በ |**ዲናው መንግሥቱ**| ፣ ***Children of the Revolution*** (በአሜሪካ እትም ርእሱ |**Beautiful things that Heaven Bears**|) ላይ የተመሠረተ የ |**ተዋዳጅ**| (ፋን) ከልብወለዱ የተጨመቀ አጭር ትርክቱ።

---

# ሡፋ እስጢፋኖስ

# በ

# አሜሪካ

------ ሐ ------

---

*በ ቢንያም ኃይለመስቀል ኪዳኔ*



***ቅድመገፅ***

የኢትዮ-አሜሪካአዊው ዲናው መንግስቱ መቀደሻ (ዴቢው) ልብወለድን፣ ይህ ሥራ ጠቅልሎ ጨመቅ ማድረግ ይሞክራል። አጠር ያለ የተዋዳጅ (ፋን) ልብወለድ ነው። ሞላጎደል የብሉይ (ኦሪጂናል) ልብወለድ ትርክቱን ይዘት አይቆርፍም። ጠቀም እሚሉ ነጥብዎቹን እንዳይዘነጉ ይሞክር አለ።

ያን ካብራራሁ፣ የየለሁብትምታ (ዲስክሌይመር) እና የማስጠንቀቂያዎች ጋጋታዎቼ ግንባርስጋ ናቸው። ይህ አሀድ (ፒስ) ሙሉ ወይም ያልተቋረጠ-ከፊል የልብወለዱ ትርጉም አይደለም። ይፋ (ኦፊሻል) አይደለም። የታዘዘ ምርት አይደለም። እጅግእጅግ ኢምንት የተዋዳጁ ፈጠራ ምቾት ላይ እንዲንፈላሠስ ተጋብዟል። በተለይ ጊዜ መቼት ፍሰቱ ሙሉበሙሉ ተቀይሮ አለ። ወጥ-ወራጅ የጊዜ ፍሰቱን ከልብወለዱ በመቃረን ፈጥሯል። እንዲሁም፤ እንደ ልብወለዱ ሙሉበሙሉ አንደኛ መደብ ሳይሆን፤ ይህኛው ስሪት አንደኛ መደብ እና ገለልተኛ መደብ ተዘበራርቀው እንደ አመችነቱ ትልሙን ይተርክ አሉ። *"ይህ ውጤት የአንድ ተዋዳጅ (ፋን) የልብወለዱ ቅርጽ ቅየራ እና አካል ቅርጠፋ የተከወነበት የመቀደሻው ኢመደበኛ ስሪት ወይም ይልቁንም ትልም ጭምቅ ነው ተብሎ እሚታሰብ ብቻ ነው።"* በመጨረሻ ደግሞ፣ እነሆ ልብወለዱን ማንበብ ለእማይፈልግ አበልሺደወል (ስፖይለር አለርት) ተገለጠ።

በመጨረሻ ስለ አላማ እንነጋገር ከተባለ። ቀለል ብሎ ያ ተሸላሚ ልብወለድ በአማርኛ እንዲነሳ እና ሙሉውን በእንግሊዝኛ ለማያነብቡት እንደ ጭምቅ (ሰማሪ) ጭምር ሆኖ እንዲያገለግል ይህን ውጤት ያንን ኢላማ አልሜለት አለሁ። ዳሩ፣ ይህ ስራ ከዋና ልብወለዱ ተመዥራጭ ትትረት አይደለም። በቀጥታ የተዘጋጀ የልብወለዱ ጭምቅ (ሰማሪ) በሌላ አሀድ ዶሴ እራሱን ችሎ ተዘጋጅቷል። በእንግሊዝኛ  የተመራረጡ ጥቅሶቹ እና የተለያዩ የተዋዳጁ ሂስአዊ ውይይቶችም አሉ። ከእዚህ አሀድ ትትረት ጎን እነዚህ የተለያዩ የትትረት አሀድዎች ለንባብ-ፍጆታ ክፍት እነሆ ናቸው። በተለያዩት በይነመረብ መካንዎች (ቀጣይ ገፅ የተዘረዘሩ) እነእዚህን መድረስ (አክሰሥ) እሚቻል ነው።፡

**፨፨፨መልካም-ንባብ፨፨፨**

የተለያዩ የልብወለዱ ትትረት ዉጤትዎቹን (ጭምቅ እና ዉይይቶች) ወይም ይህን አጠር ያለ የተዋዳጅ ልብወለድ፤ በ አህዝአዊ ስራትአቸው ከ www.academia.edu, www.archives.org, ወይም www.binyamhk.wordpress.com, ማግኘት እሚቻል ነው፡፡

**<u>ምእራፍ አንድ ፣ ደባሪ ቀን</u>**

*ታህሳሥ 1970፣ ከአስራሰባት አመትዎች ቀድሞ፤*

<u>አዲሥአበባ፣</u>

<u>የቀይሽብር ቀዉጢ ቀኖች ጅማሮ</u>

*ሰስራስደስት ሰመቱ ነው።* እንደብዙዎቹ የዘመኑ ልጆች፣ ባለ ቆፍጣና ስብእናው፣ ኩሩ ሀበሻው እና ቀጫጫው፣ ሠፋ እስጢፋኖስ። ጠበቃ አባቱ ለምሣ ቤት ተመልሶ ባለ አራት አላባ ቤተሰቡ በአንድ ላይ ተሰብስበው ይመገባሉ። ለሰዓትበኋላ ስራው ሽብሩ ወደስራ ሲመለስ፣ ዝናብ እንኳ ቢሆን እማይታጠፍ ህግ አለው። ለክረምቱ ትምህርት ስለተዘጋ ሠፋን ሁሌም መስሪያቤቱ አብሮ ይወስደዋል። እያስነበበው፣ በተግሳፅ እና ምክሮች እያበለፀገው፣ (በራሱ እየተዝናናም) ኩርማን ቀኑን ዉሎ ሲያበቃ ከመስሪያቤቱ ይወጣሉ። አባቱ በአዉቆታ (ኢንቴንሽናሊ) ባህል ባደረገው ልማድ - በፅሞናአማ የሰከነ እና አፍታች እግርጉዞ የመናፈሻ ኩርማን ሰዓት እረፍት ታክሎበት - ወደቤት ለዓይን ሲይዝ ይመለሳሉ። መሽቶ ሲነጋ የክረምቱ አዲስ ቀን ይሆንልአቸው አለ።

ዛሬ ከጠዋት ጀምሮ ቀኑን እሚያሞቅ ጠፍቶ ዝናቡም በርታ ብሎ ከታናሽ ወንድሙ ዳዊት ጋር ካርታ ሲጨዋወቱ አረፈዱ። ትንሽ ሲያባራ፤ ጓደኞቹ ጠርተውት ወዲያው ዳዊት ወደመንደር ወጣ። እናቱ ብርቱካን ደግሞ የሠፈር አዲስ ለቅሶ ስራዎችን በማገዝ ነው ያለችው። ለብቻው፤ ድብርቱ በዛ። በከፍተኛ ባይተዋርነት ቆየ። አባቱ ሽብሩ እስጢፋኖስ፣ ከጊዜ በኋላ ቤት ለምሣ ገባ። ለሁለት ተመገበው፣ መስሪያቤት እንደተለመደው አብረው አዘገሙ። በብዛት በሻይ እና ቆሎ ጨዋታ እየተደበረ እና ሀዲስ አለማየሁን ደግሞ ሲያነብብ ዋሉ።

ሲመለሡ ባለው የቀትርበኋላ ጉዞ፣ እሚናፍቀው አንድ ትእይንት ስለለመደ፣ ያ ዛሬ የከበበውን ድብርት በደንብ ሊያላቅቀው እሚችል ሆኖ ታየው። አትክልትተራ! ጭንቅንቅያለው የከሠዓትበኋላ የአትክልትተራ ጎዳና ብዙ አዝናኝ ድራማዎችን አግኝቶብአቸው ነበር። የበግ ነጋዴው ከበጎቹ የእረኛነት እስጣገባ ሲከውን፣ የአየርላዩ እና አየርባየሩ የንግድ ግርግር፣ ጫጫታ ኹካታው እና የቦታፍለጋ ግፊያው፣ በጭንቅንቁ መሀል የመኪናዎች መስተንግዶ ፍላጎት መታከል፣... ተደራርቦ ሁሉም እሚደንቅ ትእይንት ሆኖ እሚያዝናናው ነው። አሁንም ወደእዛ ሲደርሡ በግርግሩ ምልከታ ኩምኮማው ተደሠተ።

በእዚያ ተናፋቂ ጎዳና ወግ-ጠበቅ አድራጊው አባት እና ልጅ ተያይዘው በዝግታ እና ጥሞና እያዘገሙ አለፉ። እንዳሰበው መልክአ-ግርግሩ ሂደትበሂደት በደንብ አነቃቃው። በተለይ አንድግርግር መሀል አትክልት እና ቅጠላቅጠል ነጋዴውን በመደበቅ ሰርቆ ከቆስጣዎቹ እሚመገብ ፍየልን ዘግየት ብሎ አይቶት እጅከፍንጅ ፊት እግሩን ሲያዝ አይቶ ሳቅ አለ። ነጋዴው ፍየሉን ሲያስር ደግሞ የበለጠ ሳቅ አለ። አባቱ አላየም። ነጋዴው ባለቤቱን ሊያስከፍል አስሮ ሲቸረችር ፍየሉ ጭራሽ ተመቻችቶ ከጀርባ ሳይታይ መመገብ ጀመረ። ነጋዴው በመናደድ ፈትቶ ለቀቀው። ከእዛ የበለጠ ስቆ ብቻውን ለቀቀው። "ሞኝ እንዳትሆን አንተ"።

በፅሞና አጥር ዳግ-ታጥሮ መጓዙ ቀጠለ። መዝናናቱም ደግ ሆኖ ቆየ። ዳሩ፣ የበረታ ክፋት በቀኑ ነበር።

የደርግ መንግስት አዲሥአበባን እንደ እሳት እያነደዳት ነው። የወታደሮች-መንበርአዊ-ቡድኑ፣ ገና አጭር ወቅት በስልጣን ቆይቷል። በቂ ቅውሳ ግን አነባብሮ በደንብ እስካሁን አስመልክቷል። አሁንም ወደ ማዘጋጃ እንደቀረቡ፣ አንድ ሽንጣም አንበሳባስ፣ በረዥሙ እራሱን እያጮኸ ወጣት እስረኞች አጭቆ በማዘጋጃ ወደ ስድስትኪሎ መስመር ወጣ። ህዝብ ሁሉ ትኩረቱን ወደእዛ መኪና አዞረ። አሁንስ መኪናው በደንብ እየተጠላ ነው። መራራ ስራው እየተቋቋመ ነው። ወጣት ተማሪዎች ወደ ተሰበሰበው ኹካታማ ገበያ ለእማይደርስ እርዳታ እጅ አዉለበለቡ። ከአየመኪናው መስኮት-መስታወቶች በማሾከክ መትረየስ ጥይቶች የደገኑበት ወታደሮች ላይ ነጋዴ እና መአላፊአግዳሚው ሁሉ በማጉረምረም፣ ተንጫጫ። ባሱ በፈጠነ ጉዞ ሁሉን ንቆ ከነወጣቶቹ ተሠለበ። "ስንት እናት እና ቤተሰብ እያለቀሰ ያድር ይሆን?" እስከ ቅርቡ ድረስ ብዙ ተሳፋሪዎች አጭቆ ሲጭን በጋራ መሆንን እና በፍቅር መኖርን በማስገኘቱ ዉስጡ በነበረውም ንፁሕ ጨዋታ ታዋቂ የነበረውን የከተማ አዉቶቡስ፣ መደበኛ አገልግሎቱን ቀይረው ወደ እስረኛ ማመላለሻነት ይሄ እንጭጭ-ግን-ጨካኝ መንግስት ለዉጦት አለ። ያወረዳቸው ንጉሥ ያንን ማመላለሻ በጥቁሮች ለጥቁሮች የተዘጋጀ የመጀመሪያው የብጤው አገልግሎት አድርገውት ነበር። ስንት የመጀመሪያ ዝሙን ስልጣኔ እንዳልፈበረኩልን፣ ተፈንግለው ይኸው በእርግጥ የመጀመሪያው ባልሆነ የእራስ በእራስ ለራስ መጨራረሥ

ብቻ እንደሆነ ነው። ቀኑ መደበሩን ዳግ-ቀጠለ። “የብቻዬ! ብቸኛ ልጄ! አስቁሙልኝ መኪናውን!” እሚሉ እናት መኪናው አልፎ ትንሽ ቆይተው እየተከተሉት በሩጫ ወደሰፈሩ ደርሰው ማልቀስ ሲያያዙ ሰዎች በመፍራት ተቆጧቸው፤ አጽናኑአቸው። እኛም አዘገምን።

ወደ ተለመደው መናፈሻ አባቱ በለመዱት የመዝናኛ እርምጃ (ዎክ) ይዞት ሲሄድ ከፍተኛ ሦቆቃን እግረመንገድ በባሶቹ ሲከወን ከእያቅጣጫው ተመለከተ። ወደሰሜን የአዲስአበባ መዉጫ እሚጣደፉ ባሶች አልተቋረጡም። ወግ እሚያይበት የነበረው እና እሚወደው አምቦሣ ባስ ብዙ የተጨነቁ ወጣት ዜጋዎችን በእስረኛነት ሸክፎ-አዝሎ፣ ጠባቂ ወታደሮች ወደህዝብ በመስኮትዎችአቸው ጠብመንጃዎች ደግነው ወደ ሰንዳፋ እንደእሚያግዙአቸው ይታወቃል። ያን ከተማ ምን እንዳጨከነው እና ወደእራሱ ዜጋዎች እንዲህ እንዳስዞረው እንጃ! ብቻ ይሰቀጥጥ ነበር።

አባቱ ይህን የደርግ እርምጃ በዝቶ ዛሬ ሲያየው ነቅፎ በማናገር ወትሮ በፀጥታ ብቻ የእሚመራውን እርምጃቸውን ወደዉይይት ቀየረ። ወዲያው ግን በንዴት ቁጣው ሳይበርድ፣ አረፍብለው የፅሞና ጊዜ እሚያደርጉበት መናፈሻ ጋር ተቃረቡ። መናፈሻው በአንዱ የቤተመንግስት ዳርቻ ጥላ ተከልሎ የተሠራ መለስተኛ ፀጥታ እሚገኝበት የተገደበ መካን ነበር። ለአባቱ ተወዳጅ ማረፊያ ነው። ወደእዛ ቀረቡ። ተቀምጠው አየር በመቀበል እና ጥሞናጊዜ በመከወን ወደኩርማን ሰዓት ሁሌም ያሳልፉበታል። አባቱ ፀጥታን አስተምሮት “በኋላ ሳትገደድ፣ ጥሞናን በህይወትህ አንተ ቀድመህ ጋብዘህም እየው፤ ልመደው፤” በማለት በሙከራ-አስተምህሮት ያለማምደው ነበር። ያንን በጋራ ከውነው፤ ወደቤት ለአይንሲይዝ አካባቢ ይመለሡ ነበር።

አሁን ግን ልክ መናፈሻው በር ላይ ሲደርሡ፣ አንድአች በላጭ መዓት በሩ አካባቢ ተቀበላቸው። ይህም ለቃል ከባድ ነው። ሠባት በባዶ ጭቃ እግሮች የነበሩ ወጣት ወንዶች ተረሽነው እሬሳአቸው ወደመናፈሻው እንደተገባ ባለ መሬት ላይ እንደ ስጥ ተሰትሮ ነበር። ጥቂት ጎብኚዎች ቀደምብለው ገብተው የነበሩ፤ የእሬሳዎቹን ኩነት በመነብኘት ወጡ። እነሡሩ በከፍተኛ ከውታ ተመቱ። አባቱ ጥርሶቹን አለአቅምአቸው እያስጨነቀ ነከሰ። ግን ምን ያድርግ? ወደልጁ ሹክ አለው። “እዚህ ያየነው ምንም ነገር የለም! ና ወደዉስጥ እንግባ!” ይዞት ሊመለስ ካለ በኋላ ወደአሰቃቂው መናፈሻዉስጥ አዘገሙ። እሬሳዎቹ በእየአንገትዎችአቸው ‘ከሀዲ’ እሚል ወረቀት ተፅፎባቸው ነበር። የተረሸኑትን አለፉ። እሬሳ-ጠባቂውን ራቅ እንዳሉት፣ እየተቀመጡ፣ አባቱ በዝግታ አናገረው። “ብንመለስ አብዮትአዊ እሚሉት ጭፍጨፋውን እውቅና መስጠት ነው። ከቶ ያን አላደርግም! ስለእዚህ ያየነው የለም!” ልጁን አስጨከነው።

የሡፉ የመዝናናት ዕድል ከቶ ተሠረቀ። 'ደባሪ ቀን! ገና ኮሎኔል መንግስቱ ቀይ ቀለም የሞላ ጠርሙሱን በአደባባይ ሰብሮ አብዮትአዊ መልሶማጥቃቱን ካወጀ እና የኢትዮጵያ ጠላቶች ደማቸው እንዲህ ይፍሰሥ ከማለቱ ይኸው! የኢትዮጵያ ወርቅ ዕድል እና ምስኪን የድሃድሃ ወጣት እንደበጋ ዛፍቅጠል እየረገፈ ነው። እጅግ ሰቅጣጭ እይት። በጣም ደባሪ!'

አረፍብለው፤ ጎብኚዎችንም በእየቆይታው እየመጡ ጎብኝተው ሲወጡ እየተመለከቱ ቆይተው በለመዱት ሰዓት ከጥሞና ይልቅ ለአላማ ጨክኖ መጽናትን ተምረው ወደቤት ተመለሱ።

**ምእራፍ ሁለት ፤ ጥቂት እረፍት**

*ያን ምሽት አልተኛሁም።* በሂደት ደግሞ፣ የበለጠ ለተቃውሞ መዘጋጀት ጀመርኩ። ይህን አይቼ በዝምታ መቀመጥ አልችልም። ከቶ። ከቶ። ከቶ። በንጋታው፤ አባቴ መስሪያቤት እንደሄደ፣ ታናሼን ዳዊትን ለእማማ ምንም እንዳይነግር አሳውቄ ሾልኬ ወጣሁ። የሰፈራችን ቀንደኛ ኢህአፓ. አባል ነበር። ወደእሱ ፊትኋላዬን ስቃኝ ደረስኩ። እሱም፣ ቤቱ ነበር። ገብቼ ማገዝ እምችልበትን መንገድ ፈራተባ ስል ጠየኩት። ብዙ የንጽዉሳኔ (ዲሞክራቲክ) ትግል ስራዎች እንደእሚሰሩ እና ፈቃደኛ ብሆን ስራ እንደእማይጠፋ አሳወቀኝ። እንቅስቃሴዎች ስለእሚቀንሱ እሁድ እንድንገናኝ ቀጠረኝ። እኔ ግን እየተቃጠልኩ ነበር። ዓይኖቼ እምባ አቀረሩ። ጥቂት የተደበቁ የጋዜጣ ወረቀቶችን ወደአንድ አባል ለማከፋፈል እንድችል አዘዘኝ። አፅናንቶ አድራሻ ሰጥቶ ምክሮችን እና ጥንቃቄ ጨማምሮ ለግሦኝ ዕቃውን አስረከበኝ። በሰለጠንኩት መሰረት ለመተግበር ቆርጬ፣ አመስግኜ ምስጢሬ (ኮድ) ተቀብዬ ወጣሁ። እንደታዘዝኩት ለድብቅ መዳረሻአቸው ጋዜጣዎቹን አድርሼ ስመለስ ምሣ ሰዓት ነበር። ቀኑን ትንሽ ነፍሴ ሰከን ብሎ አመሸሁ።

በእዛ መሰረት ሰሞኑን በርትቼ ኢህአፓ.ን ሳግዝ ቆየሁ። ዛሬ የበለጠ ሳገለግል ዉዬ መሽቶብኛል። ከመሸብኝ እንዳደርግ እንደተፈቀደልኝ እስከጧት እሚቆዩ ወደቤቴ ብዙ የፓርቲውን በራሪወረቀቶች ዛሬማታ ይዤ ቤቴ መጣሁ። በብዙ መልኩ እያገዝኩ እና መነሳሣት እና ንቃተህሊና ብዙዎች ከድርሻዬ እያገኙ እንዳለ ትላንትና አሳወቁኝ። ያ ግብረመልስ በትላንቱ ድብቅ ስብሠባአችን የተነገረኝ ሲሆን ትልቅ ደስታ የሰጠኝ እና ለትላንትና በሰሞኑ የመጀመሪያው ደህና እንቅልፍ ያበቃኝ ብስራት ነበር።

*ዳሩ፤* ወጣቶች መገደላቸው እና እምወዳቸው ተፋፍገን በመኳዝ ፍቅርን እምናይባቸው ባሶቹም ከከተማዉጭ ተማሪ እና ታታሪ ሰራተኛዎች ማጋዙን አላቆሙም። በተለይ ከመናፈሻው የግድያ ትእይንት ጀርባ እምብዛም ሠላም አላገኘሁም። አሁን ግን ጥቂት ሠላም አለኝ። በተለይ ነገ እማደርሳቸው በራሪወረቀቶች ሰፊ ትግልን በአራዳ ክፍለከተማ እሚያነሣሱ ስለእሚሆኑ ቁልፍ ነገሮችን በመሳተፍ ማገልገሌ እየተሳካልኝ ነው።

▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪▪

### 3. ምእራፍ ሦስት ፤ ደራሽ (ሰደን) አደጋ

*ድንገት የሆነውን ለማመን ከባድ ነው። ማታ አረፍ ብለን አራትአችንም ጠረጴዛ ከብበን እራት አንደበላን ገና እጅ እንኳ ሳንታጠብ ነበር። ከየትመጡ ሳይባል ወታደሮች ዘውብለው እቤት ገቡብን። አባቴን ተሸቀዳድመው እንደነፋስ ያመልጥ ይመስል ምንም ማምለጫ ባይኖርም አፈፍ አደረጉት። ምሽቱን በመኝታ ከመዝጋትአችን ቀድሞ ይህን ማየት ቅዠት ያስመስለው አለ። በተለይ  ደከም ብሎኝ ስለነበር እና መተኛት እና የዓይኖቼን እና ጎኖቼን ማረፍ ሲናፍቁ ይህ ሲሆን፣ ከቅዠትም በላይ ሆነ። በእርግጥ ጠብመንጃዎችአቸውን ሲያነጣጥሩ ልእለቅዠትአዊ (ሰርሪያሊስቲክ) ትንግርት መሰለኝ።*

ከሁለቱ ወታደሮች አንዱ ወደእኔ እና ዳዊት እየደገነ ሌላው አለርህራሄ አባቴን ጨምቆ እያየው በጩኸት ተናገረ። “ወጣት ልጅህ ወንጀለኛ ነው የትኛው ነው? አውጣ!” ወፈር ያለው ወታደር ወደ ታናሼ ዳዊት እና እኔ ግራ እየተጋባ ተመለከተ። ሲጠቆም፤ እሚጎርሰን ይመስላል። ወዲያው ሌላኛው ዘሎ ወደጓዳ ቀረብ ያልኩትን እኔን አፈፍ አደረገኝ። በአያሌው ስደነግጥ ነብሴ እምታመልጥ መስሎኝ በእጅዎቼ ልይዛት ተመኝቼ አለምሁ። እንደተፋጠጥን ቅፅበት ቆይተን ስላላመነ፣ ትቶኝ ቤቱን ሲበረብር የተቀበልኩትን የበራሪወረቀቶች መዓት ከቦርሳዬ ሳይቸገር ወዲያው አጊንቶ አወጣቸው። ጉልበቶቼ ሳይከዱኝ ብቆምም ነብሤ ግን የለችም። የት እንደገባች አላቅም። በድን ሆኜ ነው የቆምኩት።

---

ወዲያው ሳሎን ወዳለው ወታደር ወረቀቶቹን ሊያሳይ ሲወጣ፣ አባቴ አላመነም። ምንም የእንጭጩ ትግል ንክኪ እንደእሚኖረኝ አልገመተም ነበር። ዳሩ አባቴን እንዳየሁ ወዲያው ከነከነኝ። እሱ ግን ምንም አልመሰለውም። ጭራሽ ከአይኖቹ የኮራብኝ ያክል መልእክት ተሰማኝ። ወዲያው ይበልጥ እሚያቃዥ ሁኔታ አስመሳዩን ነገር ተናገረ። “የኔ ወረቀቶች ናቸው! ከቢሮ አምጥቻቸው ነበር ጧት!” ይህን ሲል የበለጠ ክው አልኩ። ወታደሮቹ ጥቂት ተጨቃጭቀው አባቴን በአንድነት እና በእየተራ መደብደብ ጀመሩ። ከመፍዘዝ ዉጭ ምን ላድርግ። አባቴ ሆንብለው ምቱን በሠለጠኑ ወታደርዎች ሲደበደብ መቆም አልቻለም። በህግ በስርአቱ መጠየቅ እንኳ የለም። አይታሰብምም። እንደ አውሬ እንኳ አላከበሩትም። እናቴም ብታለቅስ ምንም አልራሩም። እግሮቻቸው ስር እራሱን ስቶ ተዝለፈለፈ።

ደብድበውት ሄዱ ስንል፣ ይዘውት ሊሄዱ በግድ በብብትዎቹ ተከፋፍለው በማንጠልጠል አስነሡት። እየጎተቱት ወጡ። እኛ ቤት ለብቻችን ቀረን። ለእናቴ አንደኛው ዞሮ ጮኸ። “የህግዘብ (ፖሊስ) ጣቢያ ነገ ጧት ኑ ለማንኛውም!” ብቻ ብሏት ይዘውት ሄዱ። እናቴ አለቀሰች “ይገሉት ይሆን?! እ...ምንአልባት?! ምንድነው ምናልባት?! ምንአልባት ለምን አለኝ?!” የእኔ ወረቀትዎች እንደሆኑ ከአተያየቱ ገብቷት ስለነበር ማረጋገጫ አልጠየቀችኝም።

ወዲያው በጓዳ እና መኝታቤት፣ ዕቃዎች እየበረበረች መዋከብ ጀመረች። ግራአጋባችን። ሌቱን አልተኛንም። ሲነጋጋ ድረስ ዕቃ ስትበረብር እና ቁሳቁስዎች ስታማርጥ ቆየች። የጣት እና አንገት ወርቆቿን የአባቴንም የአንገት ሀብል፣ ብቻ የተገኙ የወላጆቼ ጌጣጌጦችን ሁሉ ጨምራ ሰብሥባ ሰጠችኝ። “በል ከእዚህ ጥፋልኝ ሡፋዬ! እያየሁህ ሂድ! ሰሞኑን ስንት ወጣት ገድለዋል መሰለህ! በእየመንደሩ ለቅሦ አላልቅብሎ ሳለቅስ ስዞር ነው የዋልኩት! ወደ ኬንያ አድርጎ በእዛው አሜሪካ የገባ ወጣት ባለፈውሰሞን ሲወራ ሰምቼ ነበር። በእርግጥ እንዲያ የተሰደደ ብዙ ሰው አለ ሲሉም ሰምቻለሁ። ከምትሞት አንተም ሳታቋርጥ እግሬአውጭኝ ብለህ ተጓዝ! አምልጥ አንተም የኔ ልጅ። ነገ ወይ ደብድበውት አምኖ ወይም መረጃ አጊንተው ሊይዙህ ይመጣሉ! ሂድ ሂድ ጥፋ!” እያለቀሰች ተለያየን። ወንድሜንም ቻው አልኩት እና እግሬአውጭኝ ተጀመረ።

በድንገት ይህ ሲከሠት ይከብዳል። ባንዴ አይዋጥም። ሀቁ መራር ነው። የደርግ ከተማ አሸባሪ ክፍሉ ከእዛ የእኔቤት አይገባም ሲባል ከች ብሎ በእዛ ደረጃ ቤተሰብ ማመሠቃቀሉ እና የአባቴ መታሰር። የእኔም ለስደት መበጀት እና ድንገት ባይተዋር ስደተኛ መሆኔስ! ምኑንም አማመንዠክ እና ማብላላት ከበድ ይል አለ። አማራጭ ግን የለም! መራቅ ብቻ! መጓዝ ብቻ። በእርግጥ ብቆይ ሁለታችንም መያዝአችን ነው። ተሰናብቻቸው በሌሊት አስርሠዓት ላይ ወጣሁ።

**4. ምእራፍ አራት ፤ የ ኒል ዳይመንድ አሜሪካ**

*ጉዞዬ ከባድ ነበር።* ወደ ኬንያ ድንበር ለመድረስ የተሰጠኝን ሀብት ሁሉ ሸጨዋለሁ። ከአባቴ የእጅመታሰሪያጌጥ ብረት በቀር፣ እሱም የይሁዳ አምበሳ ያለበት በልብስ እጅጌጫፍ እሚሰካ የንጉሡ ስጦታ የነበረ ጌጥ ነው፣ ሌላ የቀረኝ የለም። በቁምነገር አባቴ "አንድቀን ይሄ ያንተ ይሆናል" እያለ እንደነገረኝ እነሆ እሱም በብብቸኛነት ተርፎኝ ሳይሸጥ ኬንያ ደረስኩ። እዚህ ስደርስ እቤት መደወል የቻልኩት አንዴ ብቻ ነበር። አባቢ አልተመለሰም። የት እንደገባ አይታወቅም። እስርቤት ምንም የለም። በሀገሩ ዜጋ ሆኖ በገሀድ ተደብድቦ ተወስዶ የት ገባ? ከቤቱ በህግዘብዎች ተወስዶ የት ደረሰ ይባላል?

---

አባቴ የገባበት ቢጠፋም ብዙ በኬንያ ስደተኛዎች መንደር ሳልጠብቅ ወደ ዉጭ ለመሄድ እድሉ ግን ቶሎ ለኔ ገጠመኝ። ወደ አሜሪካ ዘመድ ስላለኝ በቤተሰብ ዳግ-ውህደት (ፋሚሊ ሪዩኒየን) ህግ መሰረት ቶሎ ለመሻገር እንድችል አመቻቹልኝ። አጎቴ ብርሀነስላሤ ጥቂት ቀደም ብሎ አሜሪካ ስለደረሠ እሱን ለመቀላቀል ቅድሚያ ተሰጥቶኝ በረርኩ። አሜሪካ። የህልም ዓለም። የዕድል ፏፏቴዋ! ኩቶ በአጋጣሚ መነሾ፣ ከከፉ የምሽት እና ቀን ጉዞዎች በኋላ እና አንድ እረኸም በረራ በኋላ ተያየን። እንዲህ ነች ህይወት ልበል? ሳናቅደው ባንዴ ካለንበት ወዳላሰብንበት ድንገት ከች እንልባት አለን። አይ ምድር! አይ እኛ! አንዳንዴ ነገር በቀላሉ አይጨበጥም። የደርግ መነሳት፣ የወጣቶቹ መሞት፣ ሳላስበው ታጋይ መሆኔ፣ አባቴን ሳላቅ ማሳሠሬ፣ የሌሊት-ሌሊት ረዥሙ ጉዞዬ፣ ወደአሜሪካ የዞረ የስደተኛነቴ ነገር... ሁሉ በፍጥነት ተከናወነ። ፈጥኖ ፈጥኖ ፈጥኖ ሆነ።

አጎቴ ተቀብሎ ወደ አለበት ሜሪላንድ ዉስጥ እሚገኝ የድሀዎች ሲልቨር ሮክ መንደር አፓርትመንቱ ወሰደኝ። እዚያ፣ ከሀያስምንት ፎቅ ወለሎች ሀያስድስቱ በሀበሻዎች እንዳለ የተያዘ ሲሆን እንደ አጎቴ በደርግ ተሰድደው እዚህ ለመቅረት የተገደዱ ነዋሪዎች ናቸው። በሀያአራተኛው ፎቅ አንድ ጥጋት ላይ ባለሁለትክፍል መኝታቤቱ ዉስጥ አስገባኝ። "የኔ ንብረት ሁሉ ያንተ ነው። እንዳሻህ ኑር! በርታ ብቻ።" ወደእረኸሙ ሶፋ እንዳርፍ እየጋበዘ ነገረኝ። ሲመሽም አንጥፌ እምተኛበት ሆነ። ህንፃው እርጅና የተጫጫነው፣ በእየጊዜው እሚቆራረጥ አሳንሠር ያለው፣ የውጭ ቀለሙ የለቀቀ፣ ትልቅ አፓርትመንት እሚሰኝ ነው። የእሱ ክፍል ዉስጧን ግን አዲስአበባ ዳርቻ እንደ ተዋት ቤቱ ዉብ ነበረች።

በቀኖቹ ዉስጥ ድብርት ግን አልላቀቅህ አለኝ። እምፈልገው ወደሀገሬ መመለስ ነው። በስልክ እነ ዳዊትን ባገኝም ደጉ ዜና ግን የለም። አባቴ ምንም ዜናው እስከዛሬ አልተሰማም። አሜሪካ ቅፍፍ ብላኝ ቆየሁ።

ቀንን ቀን እየተካው ወሮች መቆጠር ጀመሩ። ዛሬ ሦስት ወሮች ሞሉኝ። አሜሪካንን መልመድ አልፈልግም። ወደቤቴ መመለስ አብልጮ መሻት ጀምሬ አለሁ። አባቴን ፈልጌ ማግኘት ደግሞ ግዴታዬ ነው። ዳሩ፣ ምንም ወሬው ዛሬ ድረስ የለም። አጎቴ ግን ተቃራኒውን እንድለምድ ባለማቋረጥ እያበረታታኝ ነው። "ይህን ሀገር ልመድ እንግዲህ! የአባትህን ነብስ አኩራ! ወይም ሐኪም ወይም መሀንዲስ ነው የምትሆነው። በርትተህ ትማር አለህ! አይዞህ!" አለኝ። የአባቴን መሞት በእርግጠኛነት በመዉሰዱ ተናደድኩ። ግን አማራጭ የለም። ሁሉም ያንን ተቀብሎታል። በእዛ እድሜው እንዲያ ተደብድቦ ለነገ ቢቀጥሩንም ምንም ያልነገሩን ሲሞትባቸው ወይም እረሸነውት በዛው ቀብረውት ቢሆን ነው። እናቴም ያን ጭምጭምታ እንጂ የተሻለ መረጃ እንዳላገኘች በማዘን ማታውን ደውላ አሳወቀችኝ። እጅግ እሚነካ ነው። አለምንም መረጃ ሰንብቶ መሞቱን በጭምጭምታ ማወቅ ምን ይባላል!

የፈለገቢሆን ግን የቀሩትቤተሰቦቼ ጋር አዲስአበባ ናፍቃኛለች። እየተናደድኩ ዝምብዬ መንቀዋለል ለመከወን እና ሀገሩን ለመመልከት ወጣሁ።

ዳርዳሩን ይገፎ በእየመንገዱ ስረማመድ፤ ዩም  እሚሰኝ የቻይና ዶሮ ቤት አይቼ ባህሉን ላይ ጓጓሁ እና ገባሁ። ገብቼ አንድ ጥጋት ላይ አጭር ጠረጴዛ ለግሌ ይገፎ ቆምኩ። መመገብ ስጀምር፣ የሆነ ነጭ ሽማግሌ ሰው ሳንቲም ካለኝ ጠየቀኝ። የለኝም ብለውም ደጋግሞ ደጋግሞ ይለምነኝ ገባ። ብዙ ሲያስቸግረኝ አስተናጋጁ ብዙ ተጨቅጭቃው አስወጣችው። በፈገግታዋ ይቅርታ ጠይቃኝ ዶሮዬን በልቼ ስጨርስ ወጣሁ። የአጎቴ ቃልዎችን ዳግ-አሰብኩአቸው። እሱደግሞ ያንን ቢልም በተቻለኝ ሁሉ አልቀበለውም። እዚህ መልመድ አልፈልግም። ትንፋሼ ቢችል የኢትዮጵያ አየር ካልሆነ ከእዚህ በዐድ አየሩ ባይተነፍስብኝ ሁሉ ደስ ባለኝ ነበር።

እናቴ ግን አብራ የነገረችኝ "መምጣቱን ማቀድ ቀርቶ ማሰብ የለብህም!" ብላ ነው። ሳትጠራጠር ያንን ተናግራ ስታሳውቀኝ የበለጠ ሀዘኔ በዛብኝ። ወደ እናትሀገር እና ቤት ለመመለስ ከተከለከልን የት ይኬዳል?

በእርግጥ የአጎቴ መንደር እራሱን የቻለ አንድ አነስተኛ ኢትዮጵያ ማለት ነው። ሰዎቹ ከኢትዮጵያ ያልተቆራረሡ ዝምድናአቸውን እንደያዙ ነው የተሻገሩት። ሰፊ የኢትዮጵያ ባህል አለ። እንጀራ እና ወጡ፣ መጠራራቱ፣ ቡናው እና ወጉ፣ ሁሉም ህይወት በሰፊው ህንፃ አለ። ነጫጭ ባህል ልብስዎች ለብሰው በህንፃው ወለልዎች ወደአደየጎረቤትዎቹ ሲጓጓዙ አዲስአበባ ይመስላል።

አንዳንዱ ወለል ጭራሽ በሰፊ የቤገሰብ ቁርኝት ልጅ፣ ልጅልጅ፣ ጋብቻዎች ወዘተ. ሆነው እንደያዙት እሚገኝ ነው። እስካሁን ከመንደሩ ወጣ ሲባል በስተቀር በእዚህ ህንፃ አማርኛ እንጂ ሌላም ቋንቋ ከቶ አልሰማሁም።

ከሌላዎቹ ሀበሻ ነዋሪዎች በመለየት ግን አጎቴ በባይተዋርነት በህንፃው ያለ ብቸኛው ሀበሻ ነበር። ማንም ሀበሻ እማያደርገውን ብቸኛነት ተያይዞት ቢኖርም በሁሉም ግን ታዋቂ እና ተከባሪ ነው። አዲስአበባ ከካቢኔት እና ልዑልዎቹ ጋር በነበረው ግንኙነት እውቅ እና በሀብቱም የተከበረ ስለነበር አሁንም የእዛ ማእረግን እዚህ አልተነፈገም። ዳሩ፣ እዚህ ኑሮው ጎስቋላ እንደሆነ እየተገነዘብኩ ነው። ለመኖር መኳተን ነበረበት። በሀገሩ ወደ እርስበእርስ መጨራረስ መውደቅ፤ ፈጽሞ ደስተኛ አይደለም። በእየመስሪያቤቱ ይህንን ለማሳወቅ እንደተሯሯጠ ነው። እኔም፣ አዲሱን ሀገሬን መልመድን እንድገደድ እየሆንኩኝ ነው።

---

---

**ምእራፍ አምስት ፣ አንቴ ብርሀነሥላሴ እና አሜሪካ**

*አዲስአበባ ዉስጥ ብርሀኔ መልካም ስብእና ያለው ወጣት ሳለ በደንብ የተማረ ከእሚሰኘው እጅግ አናሳ የኢትዮጵያ ማህበረሰብ መደብ ነበር።* በደንብ የተሳካለት ጠበቃ ሆኖ ህግ እና ማህበረሰብን በአዲስአበባ መናገሻ ከተማ ሆኖ ያገለግል ነበር። ያ ብቻ አልነበረም። *የንጉሡ ቀኃሥ.* ልዑልአዊ (ሮያል) ቤተሰብ ዉስጥ በሙያው የማገልገል ዕድልም ገጥሞት ነበር። ብዙ ሳይቆይ የግል ሀብትን ማከማቸት በቃ። እጅግ አንባቢ እና ተመራማሪ ከመሆኑ የተነሣ፤ ጥቂት ከመሠደዱ ቀድሞ የሆነ ወቅት ቤቱን ከአዲስ በግል ጥረቱ የመገንባት ስኬት ሆኖለት ነበር።

*ፈረንሳይአዊ ኪነህንፃኛ* (ኧርኪቴክት)፣ ፍራንክ ልዮድ ራይት ፕሬሪ *በአርኪቴክቸራል ዲይጀስት* አንድ ቅፅ ላይ ከአስቀመጠው ርእዮት-ግንባታ ተከትሎ አንድ ንድፍ በማበጀት እራሱ ቤቱን ገነባው። ከአዲስ አበባ ወጣ ብሎ በተንጣለለ 'ራንች' ሜዳ ላይ የገነባው ደልቃቃ ቤት ከከበበው ተፈጥሮ ጋር የተጨባበጠ ግንባታ ነበር። ጣውላ በደንብ ያበዛ የኮርኒስስራው እና አቧራማ ግድግዳዎቹ፣ እንዲሁም ከፊትለፊቱ የተንጣለለው እጅግ ለም አረንጓዴ ምድርን ማስመልከቱ የፍልስፍናው አካል ነበር። የቤቱ ክፍሎች እማያልቁ መስኮቶች ሲኖራቸው ከመስታወቶች እና መብራት በብዛት የተውጣጣ ቤትም ጭምር ነበር። እንዳለው ከሆነ 'ቤቱ ከከባቢው ተፈጥሮ አንድ መስሎት በመንደሩ እሚታየውን መልክአምድር ተጣብቆ ተገንብቶ ሳይታሰብ ወደከባቢው ቤቱ እራሱ መስረግ እና መሰወር አለበት። ከመልክአምድሩ ተጣጥሞ ዉስጡ መጥፋት አለበት።

እዛች ቤቱ በደስታ ለጥቂትጊዜ ሲኖር፣ ያ ከልዑልአዊ ግለሰቦች እና ልሂቃን አንጃ ያቆየው ሙያው እና ህይወቱ ግን በደርግ ተጠለፈበት። ልክ የሠፋ አባት ከተያዘበት ሁለት ዓመቶች ቀድሞ፣ በአንድ እኩለሌሊት ከመሬት ተነስቶ ተሠለበ። የቤቱ ወደ ተፈጥሮ እሚደበቅ አገነባብ እሱም አንዴ ወደ አየር እንደእሚጠፋ ጉልህ ፍንጭ ነበር። እና ቤቱን ወዲያው ወታደሮች ወረሩት። ምንም የለም። ሰራተኞች እና ዘበኞች ንብረቱን ወሰዱት እንጂ አለሁባይ ጠፋ። ዉስጡ ያለው እስኪያልቅ ተቀጣሪ አገልጋይዎቹ ኖሩበት። በኋላ የደርግ መንግስት ወረሰው። የተለያዩ የባለስልጣን አይነቶች እየተተካኩ እሚኖሩበት ሆነ።

ብርሀኔ ግን ከጠላቶቹ አንድ እርምጃ ቀድሞ ተገኘ። ወደ ሱዳን ስደተኞች መጠለያ ሌትሌት ባለማቋረጥ በእግር እየተጓዘ፤ በአንድወር ደረሠ። ቀንቀን ሀሩሩን ለማስቀደም ቁጥቋጦ ስር እየተኛ ያርፍ ነበር። በመንገድ እንደእሱ ሆነው ከተገናኛቸው ተጓዦች፣ ከፊሉ በእየመንገዱ ሂደት ሞተው አለቀባሪ ለበዪ እየተተዉ ታልፈው ነበር።

ሱዳን ከገቡት ስደተኞች፣ መራሩን የመጠለያውን ሁኔታ ለመላቀቅ ፈልገው የነበሩ አስራአምስት ስደተኞች በአንድነት ሆነው አንድቤት ተከራይተው ሲወጡ አንዱ እሱ ነበር። ቀዝቃዛ የጡብ ወለል ላይ ተጨናንቀው ይተኙ ነበር። ሲተፋፈጉ አፍንጫው ስር ከእሚሰነቀረው ካልሲ እንዳይሸተው እና ንፋስ ለመማግ ቀና እያለ በመደጋገም ሲተኛ ይታገል ነበር። ዳሩ፣ ምርጡ የህይወቱ እንቅልፎች በእዚያ እንዳለፉ ዛሬም በኩራት ይናገራል።

አሜሪካ ከገባ ጀምሮ አንድ ያልተወው ነገር ለፕሬዝዳንቶች (ጂሚ ካርተር እና ሮናልድ ሬጋን) እና ብዙ ባለስልጣኖች ጦማር መፃፉን ነው። የደርግን መንግስት ገዳይነት እና ኢህግአዊነት በመግለጥ ሰዎች ንፁሕ ሆነው ከእሚሞቱ እንዲድኑ እና የድርሻዋን አሜሪካ እንድትወጣ እየጠየቀ ይነዘንዝአቸው ነበር። መጀመሪያ ለፕሬዝዳንት ካርተር መፃፍ የጀመረ ሲሆን በጠቅላላ ይል የነበረው

> *'የኢትየጵያ ስደተኛ ነኝ፣ ሀገራችን በወታደሮች አለህግ ብዙዎች ንፁሐችን በመግደል ላይ ነች፣ ምንም ያላጠፉ ብዙዎች እየሞቱ ዜናውን እዚህ ሆነን እየሰማን ነው። ሀገራችንን ይርዷት እባክዎን።'*

ወዘተ. ይልአቸዋል። በሀገሪቷ የነበረው ጅማሮ ሁሉ ዋጋ እንዳጣም ይሰብካቸዋል። ምላሹ እሚፈልገው አልነበረም። ብቻ እሚመለስለትን ጦማር አጭቆ በስርአት በመደርደር ብር ከእሚያስቀምጥበት ሳጥን ጎን በሌላ ትንሽ ሳጥን ቁምሣጥኑ ውስጥ ያጠራቅም ነበር።

አሁን ደግሞ ሰፋን ከተቀበለ በኋላ እንዲማርለት እና ትልቅ ደረጃ እንዲደርስለት በመምከር ይታገል ነበር። በአሜሪካ እንደእሚሳካለት ተጠራጥሮ አያውቅም። ከመጣ ሦስት ወሩ እንዳለቀም፣ አስሥ የመረጠለትን አንድ ትምህርትቤት አሳወቀው።

ወስዶ ወደ *ቨርጂንያ ማህበረሰብ ኮሌጅ* በማስመዝገብ እንዲማር አደረገው። አንቴ በአለበት መንደር የሀበሻዎች ሠፈር ስለሆነ እዛ ለተሰበሰበ ስደተኛ ሀበሻ ሁሉ ብዙ ጨዋታ ስለ ሰፋ ያቀርብ ጀመረ። ሰፋ ከመንደሩ ማህበረሰብ ተለይቶ በደህና ትምህርትቤት መማሩም እሚጠቅመው እንደሆነ በመናገር የመንደሩ ሀበሻዎች ቡና ሲጠራሩ ይቀልዱበት፣ ቡና መጠጫ ያደርጉት፣ ይኮሩበት፣ መጨዋወቻ ያደርጉት ሁሉ ነበር። ሰፋም በርታ ብሎ መማሩን ጀመረ።

በአጭር ሂደት ግን፣ ሰፋ የአጎቱን ሀበሻ ጎረቤቶች እና መንደር ሰለቸ። መንደር ሲሆን ያለው አለሙ አማርኛ ብቻ እና ከሰፈሩ ሲወጣ እንግሊዝኛ ብቻ እየሆነ እየተለዋወጠበት መጨነቅ ጀመረ። አጎቱ ግን ስራውን በመጠንከር እየሠራ ሰፋንም ምህንድስና ትምህርቱን እያበረታታው እና "ቤቴ ቤትህ ነው እንዳሻህ!" ብሎ ቁልፍ ሰጥቶት በግሉ እየወጣእየገባ እየተማረ እንዲሰራ አድርጎት መኖሩን ቀጠለ።

ብርሀኔ በታክሲ ስራው ገቢውን መደጎም ተያይዞ የቆየ ነው። "አንዴ አዲስአበባ ብመለስ፣ ቤቴ ለእሚኖረው ጀነራል መኪናነጂ ሆኜ በመቀጠር በመጀመሪያ ጉዞአችን ይዤው ገደል እገባ ነበር።" ብሎ ሁሌ ይቀልድ ነበር። በተረፈ፤ በግል ጉዳይዎቹ ግን ኮስታራ ሆኖ እሚኖር ነው።

<u>**ምእራፍ ስድሥት ፣ ጓደኝነት፣ እማይሞላው ኑሮ እና ሱቅ**</u>

*ብርሀነሥላሴ ወደ ስራ እንድገባ እየወተወተኝ ጥቂት አረፍ እንዳልኩ "ይበቃሀል አሁን ስራ ጀምር!" ብሎኝ ወደ ዲሲ. ያው ይዞኝ መጣ።* ሁሉን ድርድር ጨርሶ ሄጄ መስራት ብቻ እንዳለብኝ ነግሮኝ ወደ እዛ አብረን ተጓዝን። በነጩቤተመንግስት ፊትለፊት የተገነባው የጣሊያኖቹን የ *ሜዲቺ* ቤተሰቦችን ቤት አስመስሎ እንደቆመ የእሚናገረው ካፒቶል ሆቴል ፊትለፊቴ ሲቆም በዉበቱ ተደምሜ ዉስጡም መቀጠሩ ተስፋ ያለው መስሎኝ ነበር። ዳሩ፣ ገና የመጀመሪያው ግንኙነቴ (ፈርስት ኢምፕሬሽን) ፍፁም አልሆነም።

ንቀት ያለበት ግዙፍ አለቃ ጋር ብርሀኔ አገናኘኝ። በሆቴልዕቃ ተንከባካቢነት (ቫሌት/ቤልሆፐ) መስራቱ የቤተመንግስቱን ምርጥ ዕይታ ፈላጊ ጎብኚዎችን ተቀብሎ ዕቃዎቻቸውን ወደክፍልዎችአቸው ማመላለስ ስለሆነ፤ ያ እሚከብደኝ ከሆነ አሳብ ገባው። ቀጫጫ ስለሆንኩ ከበድያለ ዕቃ ማንሳት እሚከብደኝ ከሆነ ብቻ አላሳሠበውም። ከደንበኛ እና ቤተመስተናገጃው (ሆቴል) እማልሰርቅ እና ጨዋ መሆኔን፣ እንዲሁም አምሽቼ በሌሊት ሽፍት ለመስራትም ፈቃደኛ እምሆን ከሆነም ጠየቀው። አጎቴ የጉልበት ስራ እማያቅተኝ፣ ፀባዬ ታማኝ እንደሆነ እና ሌላ ስራ እንደሌለኝ አብራራለት። እኔም ጌታዬ ብዬ ልጠራው እሱም በተመቸው መንገድ ሰፋ ወይም እንዲቀልለው ስቴቭን ብሎ ሊጠራኝ ደንብ አባቴ አወጣልን እና አስተዋወቀን። እንደመገመት አድርጎ በመጭመቅ ጨበጠኝ። ክው አልኩኝ እና በቅጽበቱ ያኔ የተመኘሁት ቢኖር ሰውነቴ በእዛ ቅፅበት ጥቂት ጠጠር ብላልኝ የእጆቹን አጥንቶች በሙሉ በሰባበርኩለት ብዬ ነበር። ጥቂት ቆየት ብሎ ለቀቀኝ። አጎቴም ያንን ሁኔታዬን አይቶ ስንወጣ ለእኔ ቢሆንም ብቻ "ባለጌ! ምንድነው እራሱን አድርጎ እሚመለከተው!" አለው፣ ከፊቱ ባይሆንም እንኳ። እንደእዛ ለነገ መጥቼ ስራ ልጀምር ተዋውለን አብረን ተመለስን።

ብርሀኔ ለራሱ ደግሞ በትርፍ ጊዜው የታክሲ አሽከርነት በተለይ ጧትጧት መስራቱን ተያይዞታል። ከሰዓት ደግሞ፣ በካፒቶል ሆቴል የፓርኪንግ አቴንዳንት ሆኖ ይሰራል። ከወር ገቢው በእየወሩ ከፊሉን ሰንጥቆ ወደሀገርቤት ሲልክ ግማሹ የኪራይ እና ኑሮ ወር መዳረሻ ያደርገዋል። ጥቂት ደግሞ በቁምሳጥኑ ባለች *ፓንፓ* ሳጥን ይቆጥባል።

ስራውን ስጀምር ሳይቆይ ከሁለት ጓደኞች ጋር ተቀራረብን። አንዱ ኬኔት የኬንያው ዜጋ ሌላው ጆጆ ወይም ጆ የኮንጎው ናቸው። ሁለቱም ብዙ ባልተለያየ ወቅት እንደእኔ አሜሪካ የደረሡ ሲሆን፣ በአካልም እንደኔ ቀጫጫዎች ናቸው። በአጭርጊዜም እጅግ እየተግባባን ሄድን።

ጆጆ ሁለተኛ ድግሪ (ማስተርስ) ድረስ ተምሮ መልካም ህይወት መገንባት ሲያልም፣ ኬኔት ደግሞ የምህንድስና ሙያውን ተምሮ እና ተጠቅሞ እንደአሜሪካውያን የተሳካለት ጠንካራ ሰራተኛ እና ስኬታማ አስተኔ-ቱጃር መሆን ይሻል። አባቱ በኬንያ ሳሉ በድህነት ኖረው የጀሞ ኬንያታን ስእል ብቻ አውርሰውት ቢሞቱም፣ እሱ ግን በመጠንከር ሰርቶ ሀብታም መሆን በኬንያም ትላላቅ ፎቆችን መገንባት እሚያልመው ነው።

ዘወትር በአመቺ መቼት ስንገናኝ ጨዋታዎችን እንከውን አለን። ያም ስለአፍሪቃአችን መጨዋወት ነው። አምባገነን መንግስቶችን፣ እና መሪዎችን፣ በማንሳት የተለያዩ ጥያቄዎችን እምንጨዋወትበት ነው። መሪውን አንዱ ሲናገር ሌላችን የየት ሀገር እንደሆነ እና መቼ ግልበጣ እንደከወነ ወይም እንደተከወነበት እንገልጥ አለን። ይህ መዝናኛችን እያደገ ሄዶ ስለአህጉራችን እምንናፍቀውን ያክል ባይሆንም በጥቂቱ እንድንነጋገርም ያደርገን ነበር። በስራ የተነሳ ብንተዋወቅም ከእለትእለት እየተቀራረብን እና እየተዋደድን ሄድን።

እቤት ስመለስ ደግሞ ብርሀኔ ከካፒቶል ሲመለስ እንገናኝ እና ስለስራ እና ትምህርት ይጠይቀኛል። ስለግሉ እንዳልጠይቅ በአክብሮኝ መንገድ ይዘጋኛል። ግን የድህ አኗኗር እንዲያ እንዳደረገው እና ባዶነት እንደእሚሰማው አውቅለት አለሁ። ህይወቱ በመኪናዎች አሽከርነት እና አስተናጋጅነቱ፣ ጉርሻ እና ዝርዝር መሸጥ የተመሰረተ ነው።

በሶፋዬ ተኝቼ እያለምኩ አድራለሁ። አባቴን እስል አለሁ። እና ቤተሰቤን እያስታወስኩ እቆያለሁ። አረፋፍጄ እንቅልፍ ይወስደኛል። የስራ እና ትምህርት ምልልሴም እየተለመደኝ ሄዷል። ከገቢያችን የተለያዩ ወጪዎች እና የትምህርቴን ከፍለን ስናበቃ እሚተርፍ የለም። ብቻ እንደብልህ ድህ ትናንሽ ነገሮች ቁምነገር ማድረግ ጀምረናል። በጋው ሰሞኑን ሲመጣ ለምሳሌ መስኮቶች ከፍተን ወለሉ ላይ አንጥፈን መተኛት ጀምረናል። መስኮቶችን ከፍተን፣ ቬንትሌተር ከፍተን እንዲያ ስንተኛ ለእኔ እሚያስደስተኝ የምሽት ወቅት ነበር። ቅዝቃዝ የለሽ ጭው ያለ የበጋ እንቅልፍ እልፍ ነበር። ለአጎቴም ያ አተኛኘት ደግ ነበር። "እንዲያ መተኛታችን በስደተኛነት ሳለ የነበሩትን የሱዳን ምሽቶቼን ያስታወሰኛል!" ይላል። ሲነጋ በጊዜ በመነሳት ተለያይተን በእየፊናችን እንሰማራለን። ዉለን ማታ በመገናኘት የተለመደ ድግግሞሽን በመከወን መኖሩን ተያይዘንዋል።

ከመጣሁ በአመቱ በቤት፣ ስራ እና ትምህርትቤት የተገደበው ህይወቴ እነሆ ተለመደ። የአባቴን ሞት መሳል፣ በትምህርትቤት ለብቻዬ እሱን እና ያሉትን ቤተሰቦቼን በመሳል እያወያየኋቸው መቃዠት ጀምሬያለሁ። ብዙ አዋያቸዋለሁ። ብዙ ጥያቄዎች በቆይታዬ ስለመጡ እማወራው አያጥርም። በትምህርትቤት ኢትዮጵያዊነቴ ከባድ ሆኖብኛል። ዝንብ የወረረው የኢትዮጵያ እረሀብተኞችን ፊት እያሳዩ ድርቅን በእኔ ላይ አስፅፈውብኛል። ግን አስተያየት ሰጪዎች ቢያስጨንቁኝም እኔ እዚሁ ከመማር እና ስራ መስራት መሞከር በቀር ምንም ስለረሀቡ እማውቀው አልነበረኝም።

በሂደት፣ አንድ አመት ተምረሀ ትምህርቱን ትቼ በስራው መቀጠል ተያዝኩ። አሜሪካንን በወጉ ትንሽምቢሆን ለምጃታለሁ። በማናችንም ህይወት አዲስ ነገር ግን እምብዛም የለም።

### *ሁለት አመትዎች በኋላ*

ዛሬ ልክ እዚህ ከመጣሁ ሦስት አመት ከአንድ ወር ሆነኝ። መደረግ እሚችለውን ሁሉ ባደርግም ኑሮ አልተቀየረም። ነፃነትም የለኝም። በተለይ በቅርቡ ደግሞ እኔን እየደበረኝ ነው። ዛሬም እንደሰሞኑ ከፍተኛ ድብርት ይዞኛል። ወደስራ እምገባው ሳልወድድ ነው። አሰልቺነቱ አሸንፎኛል መሰለኝ። ብዙ ይሰራል አርኪ ነገር ግን አይገኝም።

ብቻ እንደለመድኩት ወደ ስራ በማቅናት ለእለቱ ተመዘገብኩ። ዉሎዬን ሳጠናቅቅ በከፍተኛ መዛል ምሽቱ ተቀበለኝ። አለቃዬ ማምሸት ከቻልኩ እንዳመሽ ሲነግረኝ እምቢ ልል አልወደድኩኝም። ቆይቼ አስራሦስት ሰዓቶች በመስራት ከመሸ በኋላ ወጣሁ። ዳሩ እጅግ ዝለት እና ባይተዋርነት ከድህነቱ ጋር አላንቀሳቅሥ ብለው በስሜት ከበቡኝ። መጥተው ሦስቱም ያናገሩኝ እና "ዋጋቢስ!" ያሉኝ መሰለኝ። ድምፅ ግን አልሰማሁም። በምሽቱ ለብቻዬ ነኝ።

ከተለመደው በላይ ብዝልም ለአንድ የሁኔታው መቋጫነት ላይ ለመድረስ ቆርጬ በብቸኛነት መጓዝ ጀመርኩ። የተሰማኝ ሁሉ ወደአንዳች ግልጥ አረዳድ እንዲያደርሰኝ እብስልስል በመፈታታት መከወን ጀመርኩ።

ሌሎችን እጅ በመንሳት መቀበል እና ጓዞቻቸውን ተሸክሞ በመንከባከብ ሰውነቴ እጅግ ዝሏል። ኑሮዬ ከእንግዲህ እንዲህ መሆን ግን የለበትም። በ *ፖቶማክ* ወንዝ ዳርቻ እየተጓዝኩ ጫፉ ላይ ደርሼ ወራጁን እያየሁት ቆምኩ። ለህይወቴ ለውጥ መፈለጌን አረጋገጥኩ። አሜሪካን መረገጥኩ ሦስት አመትዎች ሄደው ጥቂት ተምሬ እና በተሸካሚነት አገልግዬ አባቴ ሞቶ ቤተሰቦቼ እሩቅ ሆነው ለእዚህ ዉዳቂ የስራ አሽከርነት ብቻዬን እዚህ መትረፌን ማመን አልቻልም። ወንዙዳር ላይ ተገትሬ እምኖርለት ነገር ያስቀመጥኩት እንዳለ ባስብም ምንም የለም። አቅማምቼ ወደቤት ከመሸ ተመለስኩ። እንደለመደው ቀድሞኝ ከገባ አጎቴ አንድ እሚያደርግልኝ ነገር ላይ እይዘው እንደነበረው አሁንም አንድ ካልሲዬን እየጠገነ እና ሁለቱንም ተለዋጭ የስራ ሸሚዞቼን በቡርሽ ሲያፀዳ አገኘሁት። ዛሬን አልፌ ነገ ልናገር ወሰንኩ።

በንጋታው ጧት ወደሆቴሉ ገብቼ ለጓደኞቼ ለመልቀቅ መፈለጌን አሳወኳቸው። በመጀመሪያ ክውታ ሁሉንም አቆማቸው። ወዲያው ጆጆ ዝምታውን ሰብሮ አበረታታኝ እና ተናገረ። "ሁላችንም ከእዚህ ወጥተን ሀብታም ሆነን እዚህ ስንመጣ ሻንጣዎቻችንን ይሸከሙ እና ወደፎቁ እነሱው እቃችንን አራግፈው እራሳቸው ያወጡናል ቆይ! አንተ ያን ቀድመህ ጀመርከው እንጂ አዲስ ነገር የለም!" አለ። አጎቴም ማታ ወሬውን ሰምቶኝ ብዙ ሊጫነኝ ሳይፈልግ እንዳልጎዳ ሁሉ በማሰብ አበረታታች አተያዩን ሰጠኝ። ጥቂት ባርፍ ብሎም ነበር መሰለኝ።

ስራውን ትቼ የሆኑ ወሮችን አሳለፍኩኝ እና በሎጋን ሰርክል *እሚከራይ* እሚል የተለጠፈባቸው ብዙ ቦዶ ቤቶች አገኘሁ። መኖሪያን በአንዱ ለማበጀት ጀመርኩ። ከአጎቴም ለመለየት ሁለተኛ የአሜሪካን ቆይታ የግልዉሳኔዬን አፋጠንኩ። ብርሀኔ ባለሁለት ክፍል መኝታቤት መኖሪያውን መልቀቅ እና በሎጋን ሰርክል የጥቁሮች መንደር አነስተኛ ሱቅ መክፈት መወሰኔን ቢሰማ ሰፊ ኢአመክዮአዊነት (አንሪዝኔብልነስ) ያገኝበታል እሚለውን አልተጠራጠርኩበትም። እኔ ግን ዉሳኔዎቼን ወድጃቸዋለሁ። ፀረገሀድአማአዊ (ኢምፕራክቲካል) ስለነበሩ ደግሞ ጭራሽ የበለጠ ወደድኳቸው። በፀጥታ ሆኜ፣ ሳልረበሽ፣ ረጋ በማለት መኖር እና በጥቂቱ-ይበቃኛል እሚለውን ነገር በልቤ ማስረፄን ባብራራለትም እሚቀበል እና እሚጠግብ ግን አይመስለኝም። ኑሮ ግን እንዲህ መሆን ስለሌለበት ለእርጋታ ማግኘት ያንን ወስኛለሁ። ሀኪም ወይም መሀንዲስ እንድሆን በሎጋን አይጠበቅብኝም። አሁንም አስቀድሞ የሆንኩት - አንድ የተናቀ፣ ድሃ፣ ጥቁር፣ ስደተኛ ባሜሪካ፣ መሆኔ - እዛ ገብቶ ለመኖር በቂ ቅድመሁኔታ ይሆንልኛል። ነፃ ያረገኛል። ያ ደግሞ አያስጨንቅም። እነእዚህን ከመሆኔ የተነሣ እሚጠበቅብኝ በሰፊው የመለወጥ ግዴታዬ በሎጋን ሰርክል አይኖርም ማለት ነው። ስለእዚህ ደስተኛነቴ እሚጨምር ነው።

መንደሩ ደግሞ አዲስአበባ አባቴ በመዝናኛ እርምጃዎች ይዞኝ ሲንቀሳቀሥ የነበረውን አካባቢ ስለእሚመስል እና በጠቅላላው የተናቀ መንደር ስለሆነ ሀገሬን እያሳሠበኝ እንድኖር ያደርጋል። በባይተዋርነት እንዳልወድቅ መፅሐፎችን ይዤ መኖርን ደግሞ

አስብ አለሁ። አንዱ ፍላጎቴ በእርግጥ በሱቅ ተሸሽጎ በንባብ ተጠልሎ መኖር ነው። የቀላሉ አኗኗር አንዱ ምሥሰው ያ ነው። ምክንያቱም ወደአሜሪካ የመጣሁት መልካም ኑሮ ፍለጋ አይደለም። አንዱን የነበረኝ መልካም ኑሮ የሰጠኝን መንፈስ ሸሽት ነው። ስለእዚህ በቀላሉ ሳልታይ መኖሩን መምረጤ ለእኔ አመክዮአዊ ነው።

ግራ የገባው አጎቴን ተለይቼ ወደ ሰፈሩ ስገባ ኬኔት ደግሞ በመንደሩ ሱቅ እንድከፍት እና በመነገድ የራሴ አለቃ እንድሆን ሀሳብ ወለደ። ብዙ ሳይቆይ ከመንግስት ብድር እንዳገኝ አግዞኝ፣ ሱቁ ተከፈተ። የሎጋን ሱቅ እሚል ስም እና እጅግ የረቀቁ ከፍተኛ ማስታወቂያዎችን በመጨነቅ ጆጆ ደግሞ አዉጥቶ አመጣ እና አስመረጠኝ። በብዙ ድካም ከእኔ እኩል የሰሩት ሁለቱም ለሱቁ ወላጅአቶች ነበሩ። የምረቃው ቀን ፈቃድ ወስደው ኬኔት ሻምፔይን ይዞ መጡ። የጋራ የመለወጥ ህልምአችን በአንተ ስለተጀመረ በማለት የነሱንም የስኬት ፈር አድርገው ተመለከጉት እና ተደሡቱ። ተስፋ እንደእዚህ ይኖረናል ብለው ወደርየለሽ ፌሽታ በመከወን የአሜሪካንን ሀብታምነት የጠነሰሡ እና ኑሮአቸው የእሚቃና መሆኑን አዩበት። የጓደኞቸው እና ያገዙት ስኬት እንዲህ ከሆነ እነሱንም የሚያገድ እንደሌለ ቆጥረው በደስታ ምረቃውን ከወኑት። የሱቁ መከፈት አናሽ ክፍያውን፣ እና አድካሚ ስራውን፣ ያሸነፈ እንዲሁም የተሻለ እሚገባው አቅምአቸውን መግለጥ የጀመረ ሆኖ ህልምአቸውን በከፍተኛ ደረጃ ያሳደገ ሆነ። ኬኔት "በአንድ ሁለት አመት ሱቁን አሳድገህ ሰንሰለት (ፍራንቻይዝ) ትከፍታለህ፤ ከእዛ እየሰፋፋ ትልቅ ንግድ ይኖርሃል!" አለው። ጆሴፍም እስከ ዶክትሬት በሚቺካን ዩንቨርስቲ ሊማር እቅዱን ያን እለት ለጥጦ ነደፈ። "ያን ዩንቨርስቲ መምረጤ አንዲት ሴት 'ካየኋቸው ሁሉ ብልህ ነህ እዛ ግባ እና ተማር ብላኛለች እና ነው!" ብሎ አብራራላቸው። ኬኔትም በምህንድስና ዲግሪ ከእዛ ማስተርስ ድረስ ለመማር አቀደ እና አሳወቀ። እሱ ደግሞ በዝምታ እያነበበ በሱቁ ሆኖ ሊኖር አሰበ።

## ምእራፍ ስምንት ፤ ሎጋን ሰርክል እና ነዋሪዎቹ

### *ከአስራስድሥት አመቶች በኋላ፣ ዛሬ*

ሎጋን ሰርክል፣ ዲሲ. አሜሪካ

*እንደዘበት የአሜሪካ ኑሮ አስርታት (ዲኬድ) ከኩርማን በደንብ አለፈው።* ጊዜ ነጉዷል። ቀን ግን ያው ነው። እምብዛም ማናችንም አልተለወጥንም። እኔ ሱቁን እንደያዝኩ ሳንቲም በመልቀም አለሁ። ብርሀኔ ጋርም ባለፉት ሁለት አመቶች የተገናኘነው ለጥቂት አስፈላጊ የነበሩ ሁኔታዎች ሁለት ሦስቴ ነበር። እናቱ ስታርፍ ከሁለትአመት በፊት ተገናኝተን ነበር። ያኔ ሰዎች ተሰባስበው ቡና በመጠጣት፣ አንዱ ሰውዬም ገብቶ እሪ ብሎ በማማልቀስ ዋልን። ቄስ መጥቶ ተሰበክን። እየተበላ እየተሰበሠብን በሦስተኛው ቀን ሂድ አለኝ። ሌላ ጊዜ ሴትጓደኛው ከኢትዮጵያ እሱ ጋር ልትመጣ ስትል አልተሳካላትም። ካናዳ ስትሻገር ዲሲ. መጥታ በሀዘን ጋብዘናት ተለያየን። እንዚህ በአስቸጋሪ ጊዜያት እምንገናኝ ቤተሰቦች ሆነን አለን። አኗኗሩ፣ ያው በተለመደ መንገድ ሲሆን ምንመደ ለውጥ የለውም። እኔም ጋር ያው ነው። የጓደኞቼም አኗኗር እምብዛም ለውጥ የለውም።

ጆጆ እና ኬኔትም ህይወታቸው በደፈናው ቢታይ ያው ናቸው። ትንሽ ለውጥ ከውነው አለተጨማሪ እድገት ግን አሉ። ተስፉ-አጥ ሆነው ግን አያቁም። የማያልቅ የአሜሪካ ህልምን የመኖር ፍላጎት በዉስጣቸው ሳይጎድል አለ። መለወጥ እንደእሚችሉ በማመን ዛሬም በትጋት ላይ ናቸው። ህይወትን እንደበለፀገው ሀገር ህልም አስመስለው ለመኖር ያስባሉ እንጂ ግን ኬኔት የተሻለ የተራመደው እንኳ ብዙም ከፍታ ግን አልከወነም። ባለፈው፣ ሦስትመት ቀድሞ ያጋዛሁት አለቅጥ አርጅታ የደከመች ቀይ ሳብ መኪናው እና አብረን ከነበርንበት ስራውን መቀየሩ ጥቂት አሻሽሎታል።

ያኔ ሽክ ብሎ መኪና ተከራይቶ ቨርጂንያ ወዳለ ዉራጅ መኪና ሻጭ እንዳጋዛው በኩራት ሆኖ ወሰደኝ። አነዳዱ በጥንቃቄ እና በፍራቻ መብራት እያመለጠው እና እያስደነገጠው ነበር። ምንም ግን አይመስለኝም ነበር። እስከእዛ ድረስ አስቀድመንም ለውርስ እሚበቁ ብዙ መሸወዶችን አሳልፈን በጣም ብዙዎች ያሾፉብን ነበርን። እዛ ስንደርስ ጥቁር ስለነበርን አልንከባከብ ሲሉን ለምነንማ አንገዛም ብሎ በመናደድ ተመለስን። በሦስተኛው ቀን ሱቄ በኩራት ገብቶ ቁልፍ ሰጠኝ። “ወተህ ለራስህ እይ!” ብሎኝ የገዛትን መኪና ፈተሽኩለት። የዛገች፣ የተመታች፣ ቀይ ሳብ መኪና። አድንቄ ሸኘሁት። እስከዛሬ በእየመንገዱ ስህተት ቢፈፅምም፣ በደስታ ካላቸው ጎራ ነኝ ብሎ ለማሰብ በቅቶ እየኖረ ነው።

ጆጆ ደግሞ ከአሁን ስምንት አመትዎች ቀደም ብሎ ወደ ኮሎኒያል ግሪል እሚሰኘው ትልቅ ምግብቤት ተዛውሯል። እዛ ሲያስተናገድ ብዙ የአሜሪካ ባለስልጣን እና ተመራጮችን ያስተናግዳል። የተረፈ መጠጥ ደባልቆ ጭልጥ በማድረግ ወደኩሽና ባዶ እቃዎችን ብቻ በማመላለስ የታወቀ ሆኗል። ከአሜሪካ ህልም ጨዋታው ቀንሶ “እንደ ኃይለስላሴ ወደማስተናግድበት ሬስቶራንት ላስተናግድህ ና!” ማለቱን አብዝቷል። “እሱ ንጉስ ተገድሎ ሽንትቤት ተጥሏል” ስለው “ሁላችንም እምንሳሣት ነን። ብቻ አንተ ና!” ይላል። ሱቄን በማመካኘት እንደቀረሁ ነኝ። ሰሞኑን ግን ምንም ስራ ስለማይገጥም፣ በሱቅ ማመካኘቴ እየከበደ ነው። ጆጆ ተስፋውን ከቶ እሚተው ባለመሆኑ ግን በተለያዩ ጊዜዎች ያጠራቀማት ገንዘቡን በመክፈል በ *ቨርጂንያ ኮሚኒቲ ኮሌጅ* ተምሯል። ለመመረቅ የማያስገድዱ ትምህርቶችን በከፍያው እያከለ በመማር፣ ስለ አፍሪቃ፣ ግጥም፣ ሀይማኖት፣ ስነውሳኔ (ፖለቲክስ)፣ ወዘተ. ያጠናል። ትምርቱን ጨርሶም ጆጆ ከኔየበለጠ ትምህርትቤቱን ይወድድ ስለ ነበር ቀኑባለፈበት መታወቂያው እስከቅርብጊዜ እየገባ ቤተመፅሐፍአቸው ገብቶ ብዙ መፅሐፎች በጠረጴዛው በመቆለል ምሁርምሁር እንደሆነ ይስል ነበር። አሁን አምስት አመቶች ያለፉ የክፍል ፁሑፎቹንም ያነብብ እና አዋቂ ለመሆን ይታገል ነበር። በተለይ *ኢንፈርኖ* እና *ዲቫይን ኮሜዲያን* በፍቅር ያነብብ እና ይሰብከን ነበር። ሲሥክር እድሉን ካገኘ፦

---

*“ከከቡ አንድ የጮራ ቀዳዳ፣ እየመጡ አየሁ ሲገለጡ፤*

*አንዳንድ ዉብ ነገሮች፣ ከአምላክ የእሚሠጡ፤*

*እና ወደወጣንበት ዳግ-እንደገና፣ ከዋክብት ወጡ፤”*

---

እሚለውን የግጥሙ ቁንፅል ስንኞች "በየቱም መቼት (ስፔስታይም) ከተገጠሙ ሁሉ የምንጊዜውም ምርጥ ግጥሞች ናቸው!" ይላቸው ነበር።

ይህን የስንኞች ቋጠሮ፣ ጆጆ ከተፃፉ ግጥሞች ሁሉ ምርጡ የሆነው ነው ይለው የነበረው ዳንቴ ከሲኦል *(ኢንፈርኖ)* ሲወጣ የተናገረው የተስፋ ስንኝ ብዙ ትርጉም ለእኛ አለው ባይ ነው። ከአፍሪቃ ስለወጡ፣ ለእነሱ ሲኦልን እሚረዱበት መንገድ ከማንም የበለጠ ቀላል ነው ብሎ ስለእሚረዳ ግጥሙ የእነሱን ሁኔታ በምርጥ ደረጃ ገላጭ ነው ብሎ ይከራከራል። "መምህሬን እኔ ያን ግጥም በተግባር አቀዋለሁ! ብዬዋለሁ።" ይለናል። ምንም ሲወራ፣ እንዲህ አያይዞ፣ የአፍሪቃ አንድ ጉዳይ ይመስላል ማለት ይወድ ስለነበር፣ በተለይ ኬኔት ያንን አፍሪቃ ናፋቂነት ነው በማለት ይጠላበት ነበር። "መመለስ መቼም አትወድም፡- 'እዛ ሄዶ አፍሪቃን እየጠሉት ከመኖር፣ እዚህ በምኞት ሆኖ ቢናፍቁት ይሻላል' ነው እምትለን መቼም!" ይለው ነበር። ዛሬም ድረስ ጆጆ ለራሱ ግጥም ማበጀት እና ማጥናቱን አያቆምም። አንድ ቀን የተማረ ብዙ እሚያገኝ አሜሪካአዊ መሆን ያልማል።

ምን ተስፈኛ ቢሆኑም፣ ቤታቸው ከከተማ ዳር ትመ. እና መኝታ እንደያዘ እንዳለ ነው። ተስፋቸው ግን በእራሳቸው ብቻ አልነበረም። ለእኔም ቢሆን ማበረታታት አላቆሙም። 'ሱቅህን አስፋፍተህ የፍራንቻይዝ ባለቤት ትሆናለህ!' ብለው ያበረታቱኛል።

ብቻ፣ እኔ ደግሞ እንዲያ በስራዬ ቋፍ መቆም ቆሜ አለሁ ከስረት እና ዜሮ ትርፍ መሀከል ዋናተኛ ነኝ። ሁሉን ትቼ በያዝኳት መለስተኛ ሱቅ ቅንጥብጣቢ ሳንቲሞች በመልቀም እንደምንም ኑሮን በመግፋት፣ ደስታን ግን ላለማጣት በመጣጣር ላይ ነኝ። ሀገር ቤት ይናፍቀኛል። ግማሽ እኔነቴ እዛ ነው። ወይም ቢያንስ፣ ነበር። ወይም መሰረቱ እዛ ነበር። እዚህ ደግሞ ሙሉበሙሉ የተሳካ መቀላቀል በማህበረሰቡ ዉስጥ አልከወንኩም። ሱቁ እሚገቡት የሎጋን ሰርክል ያረጁ ነዋሪዎች እና ከትምህርትቤት ሲመለሱ ነገር ሁሉ በችኮላ እሚታያቸው ህፃኖች ናቸው። ከጥቂት ከረሜላ፣ ቸኮሌት እና የአዛውንቶች እቃ በቀረ ሽማችም የለኝም። ብቻ ደስታን በቀላሉ ማግኘትን ግን ተምሬያለሁ።

ምስጢሩ፣ በዝቅተኛ ሂወት ተደስቶ መኖርን መምረጡ ነው። አለመጨናነቅ አስፈላጊው ነገር ነው። ህልምን መለጠጥ ይቻላል። ግን ያ ብልህ አይደለም። በእርጋታ የሰከነ አነስተኛ ኑሮ ዉስጥ ተሸሽጎ መኖርን የመሰለ ነገር የለም። ስለእዚህ ከሱቋ የበለጠ ሳልመኝ ቢቻለኝ እና ብጠነክር አነስ ወዳለች መመገቢያቤትነት (ዴሊ) ቢቻል ደግሞ ዴሊውን ወደ ሬስቶራንት ቀይሬያት መኖር ነው እምመኘው። እንደእነ ኬኔት እና ጆ ሰፊ ኢላማ አላበጀሁም። ጥቁር በመሆኔም ተንቄ ስለተገፈተርኩ ይህ አኗኗሬ እሚስማማኝ ሆኗል። እና አሁንም ቢሆን ተደብቄ እየኖርኩ ነው።

ሎጋን ሰርክል ያለው መኖሪያ ቤቴ ለኪራይ እንዲያመች የተከፋፈለ ህንፃ ሲሆን፣ አጠገቡ ሳይርቅ ሱቄ አለ። መንደሩ አንዴ ትልቅ የአሜሪካ መሪዎች ይኖሩበት የነበረ አሁን የተናቀ እና የፈራረሰ ሆኗል። በአደባባዩ የሎጋን ፈረስ ላይ የተፈናጠጠ ሀውልቱ ብቻ አለ። በጦርነቱ እነካሮሌይናን ከመቃጠል ያዳነ ጀግና ነው። በሀውልቱ ስር ግን፣ ድሀዎች ይተኙበታል። ስራአጥ እና ማንምየሌላቸው ሽማግሌዎችም ይተኙበታል። አእዋፍ ሰፍረው እየተፀዳዱ ይኖሩበታል። ማታማታ ሴተኛአዳሪዎች ይራወጡበታል። ድህነት በእየደቂቃው እንደ ተራራ እሚታይበት መንደር ነው።

ዛሬ ግን የተለየ ነገር ገጥሞኛል። ከእኔ ቤት አጠገብ ያለ ልእለቤት (ማንሽን) ፍርስርስ ብሎ አለነዋሪ ቢቆይም አንዲት ነጭ ስትገባ አየሁ። ልታስተካክለው እና ልትኖርበት ይመስላል።

ዛሬ ማክሰኞ ነው። ሳናቅ እንደህግ የለመድነው የሳምንቱ የጓደኛ-ጨዋታ ቀናችን ነው። ከስራውጭ እነ ጆጆ ሁሌ እንደምንገናኘው ይመጣሉ። እንጨዋወት አለን።

ሁለቱም ከጊዜ በኋላ ሲደርሱ፣ ሱቄን ዘግቼ ወንበር ላይ ተቀምጠን ጨዋታ ጀመርን። ሱቄ ሀያሰባት ብር ያልሞላ ሽጬ መዋሌን ከደብተሩ ተመልከተው ወቀሱኝ። መዘናጋቴን ወረፉት። ስለአሜሪካ ባህሪ እንደለመዱት ያብራሩ ጀመረ። ካልተጠነከረ እዚህ ሀገር ከባድ ነው። ታገል ወዘተ. ሁሌ እንዳሉኝ ነው። እንዲህ ትንሽ ሳገኝ ሀገሩን እንደምጠላ ደግ ካገኘሁ እየተደሰትኩ እንደምኖር ያውቋታል። ስብከታቸውን ከምሰማ ግን፣ ስለ ወጣት ነጭ ሴት በጎረቤትነት ቤቴ ጎን መግባት መጀመሯን ገለፅኩ። ሁለቱም አላመኑኝም። ሎጋን ሰርክል ያንን አይነት ሰው በጤናው ይደርሳል ተብሎ አይታሰብም። ህግዘቦች ለማስታወቂያ ማሳወቅ፣ ወይም አንድ አስተዳደር ጉዳይ አሊያም ወንጀል ለማጣራት እና መመርመር ካልመጡ በቀረ፣ እምብዛም ነጭ ግለሰቦች ወደእዚህ ድርሽ አይሏትም። ትንሽ ስለእሷ ተጨዋውተን አሁንም ከምክራቸው ለማምለጥ ወሬ ቀየርኩ።

ጨዋታችንን ወደለመድነው የአፍሪቃ ጉዳይ አመጣነው። በሂደት ያ ጨዋታችን ሰፍቶ ከአምባገነን መሪዎች ጉዳይዎች በዘለለ የስነውሳኔ ድርጅቶችን (ፖለቲካል ፖርቲስ)፣ አማፂ ቡድንዎች፣ ሽምቅ ተዋጊዎች፣ አነስተኛ የመንግስት ተቃውሞዎችም ሁሉ እየጠቀስን ሌላችን እንድናብራራ እንጫወት ነበር።

“የአፍሪቃ መንግስት ግልበጣ እና አምባገነን መንግስትነት ስለማያበቃ ጨዋታችን እማያልቅ ነው።” እንባባል አለን። አሁንም ስለአሜሪካ ባህል እና የኔ ስንፍና ሊሰብኩኝ ሆነ። በተለይ ኬኔት፣ አለቃው ለእሱ እንደእሚመው “መልካሙን ፍልሚያ እየተፋለምክ ነው!” ብሎ ስለ በርትቶ መስራት ሊመክረኝ ተነሣ። ወዲያው “ቡካሳ!” ስል የአፍሪቃ ጨዋታችንን አነሳሁ። ወደ ማውጠንጠን ገቡ። ኬኔት በሱቁ ረዥም አመቶች ወዳንጠለጠልኩተደ የአፍሪቃ ካርታ በሩ ጎን አዝግሞ ደረሰ። ጋቦንን ጠቆመ። “ስህተት!” አልኩት። ወደ ማእከልአዊ አፍሪቃ ሪፐብሊክ ጠቆመ። ትክክል ነበር። “መቼ” ስለው “1964?” “አአይ!” “ስልሳአምስት!” “ስድሳስድስት!” አልኩት። እስከዛሬ፣ ሠላሳ ሦስት ግልበጣዎችን ቆጥረናል።

ቡካሳ በአጭርጊዜ እራሱም የተወገደ፣ ገልብጦ የነገሰ ነበር። ሰውበሊታ ነበር ብለው ፈረንሳይዎች ይናገራሉ። “ጥንቆላ፣ የቤተሰብ ወሲብ፣ ሰውሙብላት፣ ይከወን ነበር!” ጆጆ አከለ። የተለያዩ የአፍሪቃ መሪዎችን መርጠን ደግሞ እንመርጠደ ነበር። ለየት ያለ ቀልደኛ ወይም የለየለት እብደት አስመልካቾቹን ለይተን እናወራ ነበረደ “ምስኪን ቡካሳ! ንጉስ ቡካሳ፣ የመከላከያ ሚኒስቴር፣ የትምህርት ሚኒስቴር፣ የስፖርትዎች ሚኒስቴር፣ የጤና ሚኒስቴር፣ የጦር ሚኒስቴር፣ የቤቶች፣ መሬት እና ዱርሀብት ሚኒስቴር፣ *የውጭጉዳይዎች* ሚኒስቴር፣ የተከበሩ ግርማዊነቶ፣ የልዑዋላዊው አለም ንጉስ፣ እና በርግጥ ባይሆንም ብቻ ግን የይሁዳ አንበሳ ቡካሳ!” በረጅሙ ማእረጉን አብራራ እና ከትብለን ሳቅን።

ስለ አዲሷ ገቢ ስንወያይ የገባችበት ቤት በጣም እንደሚገርም ተገለፀ። ብቻውን ቤቱ የኖረ ሲሆን፣ አራት ሰፊ የተንጣለሉ ወለሎቹ ከታደሱ በሰፈሩ ብርቅዬ ቤት ያደርገዋል። ስለነጫ እንዳጠና በጨዋታ ነግረውኝ አምሽተን፣ እንደተለመደው ጠጥተን ተለያየን። ሁለቱም ከከተማው ዉጭ ባለ መኖሪያ መንዘረደ ከ ቲቪ እና መቀመጫዎች በቀር በሌላቸው ቤቶቻቸው ተከራይተው ደኖራሉ። ወደእዛ ሊያዘግሙ ሳብ መኪናውን ኬኔት አስነሳ። የአደባባዩን መውጫቸውን ስተው ድጋሚ ዞሩት እና ትላክስ ነፍተውልኝ ነጎዱ።

**ምእራፍ ሰባት ፤ ኑሮ፣ ጁዲት እና ናኦሚ**

*የተሻለ ቤት መከፈል ስላቃተኝ እና በምስጢር ስለወደድኩት፣ የገባሁበት ሎጋን ሰርክል የገባችው አዲስ ወጣት ሶዶምአዊት (ጌይ) ናት መሰለኝ።* ጡቷን አጥብቃ ወደደረቷ አሥራው በጉደኛ ሁኔታ ሆና ከአዳሾች ስትደራደር አየኋት። ወዲያው የተለያዩ አዳሾች አስገራሚ ስፋት እና ግርማሞገስ ያለውን ቤት አድሰው ሊያስረክቡ ህንፃውን በሞላ ተረባረቡበት። ኪነህንፃአዊ (አርኪቴክት)፣ ጣራ ሰራተኛ፣ ቀለምቀቢ፣ በእየቅጡ ያሉት ሰራተኞች እና ሀላፊዎች ስራውን ጀምረው በምሳ እረፍታቸው ወደእኔ ሱቅ ለመመገብ ይገቡ ጀመር። አስርአመቶች በላይ በአሸሸ ሱሦኞች፣ ከፖርትላንድ በአሚዳዙ አናርኪስቶች፣ እና የኔብጤዎች እየተያዘ የኖረ ነበር። ይህ ትልቅ ቤትም ሆነ ሎጋን ሰርክል የሀይል እና ሀብት መለወጥን ምስክር የሆነ ነው። “አሜሪካ ታላቅም አይደለችም ደግሞ!” እሚል መልእክትም አለው።

በሳምንቱ ሰራተኞቹ የቧንቧ፣ ኤሌክትሪክ፣ ወዘተ. ሰራተኞች ጭምር ስራውን አፋጥነው ተያያዙት። ሰፈሩ ሲለዋወጥ ቶሎ ዴሊ መከፈቴ እየጠራቸው ሰራተኞቹን ዝግጁ ምግቦችን ሲገዙ ስለእሷ ያወሩ ጀመር። ብዙ ብር ያላት ሶዶም ሸሌ ነች አሉ። “በእየወለሉ ባኞቤት ትፈልጋለች” ደግሞ ብሎ ሌላው ነገረኝ። አንዱን ወለል ቤተመፅሐፍ እና መደርደሪያዎቹ በበር እንዲዘጉ ይሁንልኝ ብላለች። ግማሽ ወለል ደግሞ መኝታ ክፍሏ ነው አሉ። ምን አይነት ዕብድ ናት። ግማሹ ወለል ሰፊ አንድ ቤተሰብ ያኖራል።

ትንሽ ቀን እንደቆየ ከቤቴ ሽቅርቅር ብዬ ስወጣ አገኘችኝ። በጨዋ ቃል ታምራለህ ስትል ተገረምኩ እና አመሰገንኳት። ሰርግ እንደምሄድ ነግሬያት ተዋወቅን። ጁዲት ነው ስሟ። ስለ አማርኛ ዮዲት ነግሬያት ከሷ በላይ ተማረከችበት። አጠገቧ የነበረች ከጥቁር አባት የተወለደች ህፃንን ልጄ ብላ አስተዋወቀችኝ። ናኦሚ ስሟ ነው። ሂሳቡን ባልችለውም ሰርጉን ለማክበር ለግሌ ታክሲ ቀጥሬ ስለነበር ተለያይተን ሄድን። ብርሀኔን አጊንቼው በርቀት ከቤተሰቦቼ አዲስአበባ ይተዋወቀ የነበረ ሰውን ዘመድ ሰርግ ተሳተፍን።

በሁለት ወሩ የቤቱ እድሳት የበለጠ አድጎ ለመግባት እሚፈቅድ ሆነ። ጁዲትን ያን ሰሞን በሰፈሩ በሰፊው እመለከታት ጀመረ። በመናፈሻው ሀውልቱ ስር ካሉት አግዳሚዎች በአንዱ ተቀምጣ የከበባትን አለም በመናቅ በጋዜጣ ንባብ ትጠመድ አለች። አንዳንዴ ወደ ሱቄ ትመጣ እና ወተት እና ከረሜላዎች ለልጇ ትሸምታለች። በሂደት ስለሰፈሩ፣ ስለአየርንብረቱ፣ ልጆች ታወራኝ እና እንነጋገር ጀምርን። ከሩቅም ስታልፍ ሰላምታ ትሰጠኝ እና ታልፍ ጀመረች። በመንደሩ፣ ወዲያው ለነገሩ በሁሉም ታዋቂ ሆነች። ከነጭነቷ በዘለለ፣ ጠቆር ያለችው ልጇ በመናፈሻው አግዳሚ ይዛት ስትራመድ ወይም በእጇ ይዛት በጎኗ ሲሄዱ ወደአይን ይገቡ ነበር።

ጎረቤቴ የሆነችው ባሏ ሞቶ በእርጅና ለብቻዋ እየሠለቻት እምትኖረው ሚስስ ዴቪሥ ስናወራ ተደብቃ ስታየን ብዙ ጊዜ ገጥማኝ ነበር። አሁንም ከቤት ስወጣ ማን እንደሆነች እና ግንኙነታችንን ፊቴን እያስተካከለችልኝ ጠየቀችኝ። “ሰፈሩ እየተለወጠ ስለሆነ የገባች ናት!” አልኳት። በእርግጥ ሰፈሩን አሻሽሎ ለመነለር ብዙዎች እና መንግስትም እየሞካከሩ ነው። “እንደኔ ያላረጀ ወተት አምጣልኝ ለማታዬ! ሱቅ ስትውልም ተጨማሪ ወሬ አድምጥ አለመረጃ አይኖርም!” ብላኝ ጉንጮቼን ስማ መርቃኝ ተለያየን።

ሱቅ ናኦሚ ለብቻዋ መምጣት ጀመረች። እቤት ከእናቷ ስትጣላም እየሮጠች መጥታ እኔሱቅ ትደበቃት ጀመረች። እናቷ ደንግጣ መጥታ ልጇን ስትጠይቅ መኖሯን ነግሬ ከውታዋን “ሁለተኛ እንዲህ እንዳታረጊኝ!” ብላ ተቆጥታ ትወስዳታለች። እኔ ጋር ከትምህርቷ መልስ ዉላ ለአይን ሊይዝ ሲል ወደቤቷ ማዘገም ለመደች። በጣም እየተቀራረብን ሄደን፣ የተለያዩ ወሬዎችን ትቃርምና ትነግረኝ ነበር። “እዛኛው ቤት አጠገብ አንዱን ልጅ ሲነፈንፉት አየሁ ዛሬ!” “እዛ ትልቁ ቤት ፊትለፊት አንዱ ልጅ በራቸው ላይ ተደብቆ ሲሸና ዛሬ አየሁት!” “ሁለት ልጆች በእየአፋቸው ተያይዘው ሲሣሳሙ አየሁ!” “ጎረቤትህ ያሉት አሮጊት አስፓልቱን ዛሬ ጢት ሲጠርጉ ነበር!” እማትነግረኝ ወሬ የለም።

ገና አስራአንድ አመቷ ቢሆንም በጣም የተገነባ እዉቀት እንዳላትም ልታስመሰክር ብዙ ታናግረኛለች። የሪፐብሊካን የውጭጉዳይዎች ትልምአግጣጫ (ፖሊሲ) የወደቀ እንደሆነ ሁሉ ዘና ብላ እንደምታውቅ ትናገራለች። “የእስራኤል እና ፍልስጤም የድርድር ሁለትዮሽ መፍትሄ ግድ እሚለው ነው!” ትላንትና አለችኝ። ዛሬ ደግሞ “ስለ ኤችአይቪ ኤድስ በቂ ነገር እየተደረገ አይደለም!” እሚል እይታዋን አጋራችኝ። ብቻ ብዙ እያናገረችኝ ስንጨዋወት እየተደሰትኩባት ሄድኩኝ። እንደሽልማት ከረሜላ እየሰጠኋት ቤቷ መመለስም ለምዳለች።

ድንገት ግን እናቷ በሩጫ መጣች። “ናኦሚ እዚነች?” “ሌላ የት ትሄዳለች ብለሽ?” አልኳት። “ኡፍ!” ለካ አንድ ጥቁር መንገድ ላይ አጊንቷት ቁላውን አውጥቶ “ጥቁር ወሸላ ትጠቢያለሽ?” ብሎ ትንኮሳ አድርሶባት ነው። ተናድዳ ስትናገር ናኦሚ መስደብ እንጂ ሮጣ መምጣት እንዳልነበረባት አሳወቀቻት። የመንደሩን ታዳጊዎች ሲለካከፉ፣ የዱርዬ (ጋንግ) ምልክቶቻቸውን

ሲያስመለካከቱ፣ ሲደባደቡ ትመለከታለች። ግን ህይወትን ከላይከላይ ባለማካበድ መቀበል እንደሚገባ በተፈጥሮ ስለተማረች በቀላሉ አልፋቸው በኑሮ-ትጓዝ ነበር። አሁንም መልሷ ነገሩን ማቅለሏን አስመልክቶን እኔ እና ጁዲት ተያየን።

ተለይተውኝ ወደቤት ይዛት ሄዳ ከሰያት አስራአንድ ሰዓት ከሆነ ግድ ቤት መግባት እንዳለባት እና ስትቀያየማትም በቤት ዉስጥ ባሉት ሰፊ ክፍሎች አንዱን መርጣ ልትደበቅ በጥብቅ ማስጠንቀቂያ ተነጋገሩ። ለካ ሠፊ ቤት ትፈልግ የነበረው ተቀናጥታ ሣይሆን፣ በፊትም ሲኖሩ ናኦሚ ስትናደድ ወደዉጭ ለመደበቅ እየሮጠች ስላስቸገረች ልጇ እንዳትጠፋባት ወይ እንዳትጎዳ በማሰብ ብትናደድ እንኳ ከቤቱ እንዳትወጣ እና አንድ ቦታ እንድትደበቃት ነፃነቷን ጠብቃም ላትጨፈምቃትም በማሰብ ነበር። እኔም ሱቄን ሽራፊ ሳንቲሞቼን ብቻ በቀኑ ሰብሥቤ ወደቤቴ መሸት ሲል ገባሁ። የእነጁዲት ቤት እጅግ ዉብ እና በእየፎቁ እሚበራው መብራት የታደሰቤቱን በግርማሞገስ ከሰፈሩ አንደኛ ያደረገው ሆኗል።

በንጋታው፣ ዛሬ ደግሞ ልጇን ትምህርትቤት አድርሳት ስትመለስ ወደሱቄ ገብታ ተገናኝተን ስለቤተሰቤ ጠየቀችኝ። ብቸኛ መሆኔን እና ኢትዮጵያ እናት እና ወንድም እንዳሉኝ ነገርኳት። እሷ አስተማሪ መሆኗን አሳወቀችኝ። የአሜሪካዊያን ታሪክ እና ፖለቲካ ላይ አተኩራ በፖለቲካሳይንስ መምህርነት ታስተምራለች። "የታሪክ ጥላቻ አለብን" በማለት ታብራራልኝ ጀመረች። "ያለፈውን እንፀየፋለን። ሁሌ አዳዲስ ነገሮች እናዘወትራለን። የመንደሩን ወሬ ስትጨርስ ደግሞ የጋራችን የፈጠራ አለም ጀመርን። ሁለት ጡጣዎች በእዚህ ምናብቴ (ፋንታሲ) አለም ከተትን። "ሱቅ አላቸው" አለችኝ። ተስማማን። "የጫካውን ቅንጡ ማህበር (ፖርቲ) ያዘጋጇሉ፣ ሄነሪ እሚሰኝ ሹፌር አላቸው በእሚለው ተግባባን። ሄነሪ ከፈለግነው እኛን ማገዝ እንዳለበትም ወሰንን። ሄነሪ እሚሰኘውም ሾፌር የቅዠቱ መሪ ሆኖ በሱ ስም በእየቀኑ ብዙ ያወሩ ጀመር።

ያን ሰሞን የጦጣ ሹፌራችን ሄነሪን በደንብ አነሳነው። ከረሜላ አቅርቦት ሲያልቅብኝ፣ "ሄነሪ አላደረሰልኝም!" አልኳት። እሷም በንጋታው ሱቄ ሳትመጣ ቆየች እና በቀጠለው ቅዳሜ ጧት ሳልከፍት ገና በሩ ላይ ስትጠብቀኝ አገኘኋት። "ትላንት የቀረሁት ሄነሪ አርፍዶ ስላላመጣኝ ነው!" አለች። "መጥቶ ነበረ እዚህ!" "እኔን ሲፈልግ?" "አዎን። ሲሄድ ትንሽ ከፍቶት ነበር"

በማግስቱ ደግሞ መፅሐፎችን አንብባ በአጭሩ በሙቶ ቃሎች የጨመቀቻቸውን ጭምቅ ሀሳባቸውን ታነብብልኝ ጀመረች። ለኔ ብላ ያንን ማድረጓን አደነቅኩ። ቤቷ እምቶስደው ከረሜላ ሽልሜያት ያየችውን ወሬም በምረቃት አክላልኝ ተለያየን።

በንጋታውም ከትምህርት መልስ እናቷ ጋር ከመሄድ ወደእኔ ገብታ ጋዜጣ እንዳዋቂ አንብባ መፅሐፍ አሳጥራ ሀሳቡን ያዘጋጀችልኝን ደግሞ ነግራኝ ልትጨርስ ስትል እናቷ መጣች። በማርፈዷ ቆጣ ብላ ጥቂት ተጨዋውተው ወተት ሸምታ ሄዱ።

በንጋታው ዉሎዬ ደባሪ ነበር። ኬኔት ደውሎ ቀሰቀሠኝ። ሰዓቱ ቢረፍድም አሌድኩም። ወደሱቅ እንድሄድ አስጠነቀቀኝ። እዛ ሲደውል የለሁም ማለት ነው ተናዷል። ሁሌ እሚደውለው አውቆ እዛ ነው፣ እንድበረታ ለማረጋገጥ። አርፍጄ ከፈትኩ። በጣም ብቻዬን ቆየሁ። አስር አመቶች አለፈው ሱቄ። ትርፉ ግን ዜሮ ብጤ ነበር። ባይሆን ዛሬ በደንብ ሰግን የታየኝ እዉነት ግን ነበር። ሎጋን ሰርክል ከ ሠላሳ አመቶች በፊት በመውደቅ እና በድህነት ተመትቶ ቆይቶ ከ አስር አመቶች ወዲህ ግን እየተለወጠ እንደሆነ በመንቀራፈፍ ስራመድ አስተዋልኩ። በተለይ የጁዲት መግባት ደግሞ እሚያብረቀርቀው ቤቷን አስመልክቶን የበለጠ መንደሩን ነቃ አድርጎታል። ሰሞኑን በእርግጠደ የበለጠ መንደር-ማሻሻል እሚል የመንግስት ጉዳይ ወደእዚህ መንደር ሊዘልቅ እንደሆነ ሲያወሩ በጥቂቱ ሱቄ ሰምቼ ነበር። መንደሩ የበለጠ ይለወጠደ ይሆናል።

ባተዋር ሱቅጠባቂነቱ ግን ደንበኛ እስኪመጣ ከፍተኛ ብቸኛነቱ ዋጠው። ለእዚህ መሠል የባይተዋርነት ጊዜ ደግሞ፣ ከድሮ ጀምሮ እሚከራያቸውን መጽሐፎች የማንበብ ልማድ ስለነበረው፣ አሁንም ያን ማድረግ ተያያዘ። ጀይ በስጦታ የሠጠው የ ቪ. ኤስ. ናይፓውል *ኤ ቤንድ ኢን ዘ ሪቨር* የተሰኘ አለምአቀፍ ተሸላሚ እና ዕውቅ ልቦለድን በማንበብ ብቸኛነት እና ፈተናውን ለማስወገድ መጣር ጀመርኩ። ልብወለዱ ሲጀምር ገና ***"ምድር እንደሆነው ሆኖ አለ፤ ሰነፍ የሆኑ ሰዎች፣ እራሳቸውን እና እንዲሆኑ የፈቀዱት፣ ምንም ቦታ በዉስጡ የላቸውም!"*** እሚለው እጅግ በሰዎች ዘንድ የተወደደ ጥቅሡ ነው። "እራሱን የማይለውጥ ባለበት ይቀራል!" በእሚለው መነሻ አረፍተነገሩ ብቻ ሣይሆን ጆጆ እንዳነብብ ስጦታ አድርጎ የሰጠኝ ገፀባህሪውን ነጋዴ ሳሌምን እምመስል ስለመሰለው ነበር። ሱቄ ባያተርፍም እናቴ እና ወንድሜ ድጋፌን ስለማይሹ ብዙ ግን ሳልጨነቅ እንዲህ አነብብ ነበር። ጥቂት ብር መላኩ ግን አሜሪካ እርቆ የመኖሩ እናት እቤት ያለመገኘቱ አንድ አመክዮው ነው። እቤት የሌለ ለይስሙላ ብር ከላከ ቢርቅም ግዴለም ይባላል። ዳሩ፣ እናቴ ለኔው ብር እምትልክበት ጊዜ ሁሉ ነበር። ጥቂት ሳነብብ ቆይቼ መሸ።

ጓደኞቼ እነኬኔትም በጊዜ መጥተው ሱቄን ዘጋሁ። እንደለመድነው ተቀምጠን መዝናናት ጀመርን። ኬኔት የተለመደ የአለቃውን 'ተፋለም እና ህይወትን በደንብ ለውጥ፤ ይቻላል' አባባል እየደገመ አበረታትቶኝ በደንብ መሸት ሲል ውጭ ወጥን በመጠጣት ለመዝናናት ተነሳን።

የገባንበት መሸታቤት ዉስጥ ሴቶች ይመጡ እና ይቀላቀሉን ጀመር። በሂደት ያ፣ ወጪ አበዛብን። የቀን ሙሉ ገቢዬ ሊያልቅ እና ልከስር ነው። ዘፈን እየደጋገምን ስናዘፍን ቆይተን በእዘፈኑ ዳንስ የሴቶቹ መጠጥ ወጪ በዛ። ስማቸው ሴቶቹ ከናገሩት ከግሪክ እና ሮም አፈታሪክ የተቀዱ ነበሩ። "ቬነስ፣ አፍሮዳይቴ፣ እና አፖሎኒያ" አሉን። ኬኔት ከንፈሩን ምጥጥ አድርጎ አይኖቹን ወደሰማይ አድርጎ በሰከረ ደስታ እየተቅለሰለሰ "በጣም ቆንጆዎች ናቹህ!" አላቸው። ብራችንን ግን ጨረሱት ብዬ በልቤ ሳሥብ፣ ዳሩ፣ ሌሎቹ ከፍለው በሙዚቃአችን ተደሰትን።

መዝናናቱን ጨርሰን በእኩለሌሊት ሰፈር እንቀይር አለን። የነጩን ቤተመንግስት ባጠገቡ ስናቋርጥ ተመለከትነው። ሞቅሞቅ ቢለንም የነፃ ሀሳባችን ግን አይደበቅም። "አሁን ስለእዛ ቤት የገባኝ ነገር ቢኖር የኔ አይደለም እሚለውን ነው!" አልኳቸው። "ብዙ ከእዛ መጠበቁም ተገቢ አልነበረም ሲጀምር!" የትልልቅ ሰዎች የገናአባት (ሳንታ ክሎዝ) ነው እቁላላማው ቢሮ ያለው ሰው። ሁለቱም ነቀነቁ እራሳቸውን። ወደ ሌላ መሸታቤት ስንገባ፣ ከ ሥላሳ አመቶች በኋላ መንደሩን የተቀላቀሉ ነጭ ወጣቶች እና የናይጄሪያ ወጣቶች በአንድነት ሲጠጡ አስተዋልኩ። እኛም ተቀምጠን፣ በብርክፍያ ዘፈን ከሚያጫውተው አንቀሳቃሽ (ማሽን) ሙዚቃ ከፍተን ስናጫውት *የአብዮቱ ልጆች* እሚለውን ዘፈን መረጥን።

እዚህ ሀገር እንደመጣን በሁለተኛው አመት ገና የአቢዮቱ ልጆች ነን እሚለውን ዘፈን ሰምተን እኛም የአቢዮቱ ልጆች ነን አልን። "ታላቅ ለመሆን እንዲሁም የጭቆና መንገዱን ለማሸነፍ" በሚያረጉት ጥረት ይህ አጋዥ እና ገላጭ ዘፈን እንደእሚሆን በማሰብ ከእዜኔ ጀምሮ እንወደው ነበር። አሁንም ደጋግመን ሰማነው። እየተቀየረ ባለው ሰፈር በሌሊት ተለያይተን ወደሰፈሬ አዘገምኩ።

<u>**ምእራፍ ሰባት ፤ ያው-ኑሮ ፤ የጁዲት እራት እና የሱቄ ነገር**</u>

*በታንክስጊቪንግ ቀን ዋዜማ፣ በጁዲት እና ናኦሚ የእራት ግብዣ ጥሪ ተደረገልኝ፡፡* አርፍዶ በመከፈት አምሽቶ በመዝጋት እምታወቅ ብሆንም፣ ሱቁን ከለመድኩት በተለየ ለመጀመሪያ ጊዜ ሳይመሽ ያኔ ነበር የዘጋሁት፡፡ ቤቴ ስዘገጃጅ እና የለሽአንከን ምሽት ለማሳለፍ ተፍተፍ ስል፣ የአባቴን ዉርስ፣ የቤተሰብልብስ-እሚመስል የኢትዮጵያ ባንዲራ ያለበት ጌጡን መጨመር እንዳለብኝ አሰብኩ፡፡ ዛሬ ካልለበስኩ እና የአባቴን መንፈስ ካላኮራሁ የት ምን እሚሠኝ ነገር ነው፡፡ ሱፍ ብለብስም መልኬ ግን ወጣት አልሆን አለኝ፡፡ ግንባራምነቴ ከምፈለገው መጠን በልጦ ታየኝ፡፡ ከመንደሩ ሁሉ የሃብታም-ሀብታሙ ቤት ምርጥምርጥ እይታ እንደነበረው፣ አሁንም የእነጁዲትም ምርጥ ቤት ነበር፡፡ ናኦሚ ሌላ እንግዳ ስለማትወድ እና የመጀመሪያው የአዲሱ ቤታቸው እንግዳ ስለነበር አመስግናኝ ተቀላቀልኳቸው፡፡

የፖለቲካል ሳይንስ አስተማሪ ሳለች የስነምጣኔ ፕሮፌሰር የሆነው ባሏ ጋር ተገናኝታ ናኦሚ መወለዷን ገለጠችልኝ፡፡ አሁን ይህ ግለሰብ በእዚህ የለም፡፡ በእየአመቱ ሀገር እየቀያየረ ሲያስተምር እንዳገኛት እና የሞሪሸስ ዜጋ መሆኑን፣ በጣም ጎበዝ እና እውቅ አስተማሪ እንደሆነ፣ በሂደት እንደተራራቁ እና አሁን እንደማይገናኙ አከላ ዘረዘረችልኝ፡፡ አምና አቴንስ ካቻምና ናይሮቢ፣ ስነምጣኔ አስተምሯል፡፡ ዘንድሮ ጀርመን ነው፡፡ ሁሌ ተሽከርክሮ እሚያስተምር ነው፡፡ የተገናኙት ባስተማሪነታቸው አማካይነተደ ከሞሪታኒያ መጥቶ እዚህ ዲሲ. እያስተማረ ባሳለፈበት ጊዜ ነው፡፡ ልጅ አጊንተው ከቆዩ በኋላ ግን፣ ግንኙነታቸው ሻከረ፡፡

አያድ ከልጇ ጋር ትቷት እንደጠፋ እና ከከተማ ከተማ ተዛውራ አሁን ሎጋን ሰርክል እንደመጡ እና አስተማሪነት ህቅ እንዳላት ነገረችኝ፡፡ ምክንያቱም እንዳለችው ከሆነ ተማሪዎቼ ሁሌ እድሜአቸው በያመቱ እኩል የሆነ ነው! "እሚያድጉ ፊቶች ተመሳሳይ ባህሪዎች" አለች፡፡ እነሱን ባለማቋረጥ እያየች በአስተማሪነት መቀመጥ እንደሰለቻት እና አስተማሪነትን መምረጧ እማያረካ እና እሚገርማት እንደነበረ አሳውቃ አጫወተችኝ፡፡ ምንም ብታወራኝ ግን፣ ከቶ በደመቀ እና የሀብታምነት ጥግ በሆነ ቤት ገብቼ የአኳኋኔን-ነገር ላለማበለሻሸት፣ አበላሌን ለማሠማመር፣ ነገሬሁኔታዬን አሠማምሬ ለመገኘት እጣጣር ነበር፡፡ ቀጥላ ስለ አሜሪካ የታሪክ ጠይነት ታስተምረኝ ጀመረች፡፡ "የታሪክ ፈር በመቅደድ (በቦንብ፣ በባቡር ሀገሪቷን መሰንጠቅ፣ ወደ ጨረቃ በመመንጠቅ፣) አንደኛ ነን፣ መልሰን ግን ታሪኩን በመንገሽገሽ ነው እምንመለከተው፣" አለች፡፡ ተመግበው ቆይተው፣ በመጨረሻ ቤቷን አስጎበኘችኝ እና ብዙ ክፍሎች መኖራቸው፣ ናኦሚ ስትቦሣጭ መሸሿን እንዳስቀረ ነገረችኝ፡፡ በመጨረሻ፣ ብዙ ተጨዋውተን ሲያበቃ፣ ናኦሚን ከተኛችበት ተመልከታት ተመልሳ ወደእኔ መጣች፡፡ ለቅጽበት ሳም አደረገችኝ፡፡ ከዛ ቤቴ ገብቼ በጊዜ እንዳርፍ  ሸኘችኝ፡፡ ደስ ብሎኝ ብወጣም፣ እቤቴ ስገባ ግን የኔ ዉልቅልቅ ያለ ዉስን ኪራይቤቴ እጅግ አስጸየፈኝ፡፡ እንደምንም ግን ተቀበልኩት፡፡

በንጋታው ኬኔት እና ዮሴፍን ቋምጩ በመጥራት አጊንቼ፣ በቼዝ ጨዋታዎች ተከብበን እንጨዋወት ጀመርን፡፡ በጨዋታው መሀከል ስለዮዲት ጋር መሳሣሜ ስናገር፣ "ግዴለም በአሜሪካ ስትኖር ሃያ አመቶች ሊሆንህ ነው፡፡ ነጭ መጥበስ አለብህ!" ብለው አበረታቱኝ፡፡ ጆጆ በኮንጎ የሃብታም ልጅ ሆኖ ሲኖር፣ ሞቡቱ ሙሉኛ እስኪያከስራቸው ከድሃ የቼዝ ተጫዋች ጓደኞቹ ሁሌ ይጨዋወት ነበር፡፡ አሁንም ሲጫወት እሚችለው የለም፡፡ ኮንጎ ሳለ አንደ ፒስ ኮርፕስ ከመጣች የቦስተን ነጭ ሴት ጋር ጥቂት ጓደኛነት እንደሞከሩ ጨዋታውን አሁንም እያሸነፈ ነግሮኝ እንድገፋ አበረታታኝ፡፡ አሁን ግን፣ ወፍሮ ብታየውም እንደእማታውቀው፣ ካቆሙበት መቀጠሉንም ያሰስቡበት እንዳሎ ገለጠልን፡፡ እና በጁዲት ጉዳይ አበረታትተውኝ ብቻ ተለያየን፡፡

ስመለስ በ 24 ሰዓት የቤተመፅሐፍ አገልግሎት እሚታወቀውን አቅራቢያ የነበረ ይፋ ቤተመፅሐፍ (ፐብሊክ ላይብራሪ) ጎራ አልኩ እና ጎበኘሁት፡፡ ጁዲት ማከማስተርሰንን ፈለግኩኝ፡፡ በአስተማሪነቷ የደረሰችውን አንድ መፅሐፏ *'አሜሪካስ ሪፑዲዬሽን ኦፍ ዘ ፓስት'* እሚል እና ጥቂት ተያያዥ መሰል መከራከሪያ አጫጭር ፅሑፎቿን (ስለታሪክ እና ፖለቲካ መከራከሪያዎቿ ናቸው) አገኘሁ፡፡ እዛው እንዳለሁ ጥቂት ማንበብ ጀመርኩ፡፡ አፃፃፏን ወድጀው ሳላስተውለው ብዙ ሳነብብ ወደንጋት ተቃረብኩኝ፡፡ በጠቅላላው ጨካኝ እምትሠኝ ወይም እጅግ-ጥብቅ ሊቅአዊ (አካደሚክ) ነች፡፡ የቀረኝን እቤቴ ለመጨረስ መፅሐፉን ተውሼ ወጣሁ፡፡

በንጋታው ሱቄ ረፈድ አድርጌ ተነስቼ ገባሁ፡፡ ብቻዬን ስሆን እንደማደርገው የተዋስኩትን መፅሐፍ እያያዝ ቀጠልኩ፡፡ እስከ አመሻሹ ብቻዬን ሳነብብ ያቋረጠኝ ቢኖር የአንድ ደንበኛ የታሸገ ዉሀ ፍላጎት ብቻ ነበር፡፡ ገበያ የለም፡፡ እነ ናኦሚም፡፡ በጊዜ መውጣት ሳሥብ መፅሐፌን ልጨርስ ትንሽ እንደቀረኝ አስተዋልኩ፡፡ ማንበቤን መልሼ ተያያዝኩት፡፡ ማታ ስጨርሠው፣ አፃፃፏ ለማለት የፈለገችው እንደሆነ የተማርኩት የአሜሪካ ታሪክ ምኑም እሚበቃ አይደለም እሚል ሀሳቧን ነው፡፡ የኤመርሰን እና አስራዘጠነኛው ክዘ. በጠቅላላው ወዳጅ ነች፡፡ አንድ የቤት ስራ ግን ስለሠጠችኝ ወደቀጣዩ መጽሐፍ ፍለጋ አደን መሰማራት አለብኝ፡፡ ጨለም ብሎ ስወጣ ወደ ቤተመፅሐፉ አዘገምኩ፡፡ ከመለስኩ በኋላ የጠቀሰችውን መፅሐፍ ፈለግኩ፡፡ የለም፡፡ ባለሙያዋን አማከርኳት፡፡ አንድ ቤተመፅሐፍ ጠቆመችኝ፡፡ እማይርቅ ስለነበር በባቡር ተሳፍሬ ደረስኩ፡፡ እዚያም መጽሐፉ

የለም። ግን ሌላ መፅሐፍቤት ተጠቀምኩ። ቤት ከምመለስ ብዛዝ ብዬ አሰብኩ። አራት ሰዓት ስለሆነ መንገዱ ጭንቅንቅ የለውም። ስለእዚህ ደፍሬ ተጓዝኩ። እዛ መፅሐፉን አገኘሁት። ዳሩ እማይገኝ ስለነበር መዋስ አልችልም። አራት እዚያው ሰፈር በልቼ ለማንበብ ገባሁ። በንባቤ አረፋፍጄ ጧት ወጣሁኝ። ይህን ያደርግኩት ለምንድነው? እንደ ተጨናነቀ ተማሪ ማንበቤ ድንገት አንድ ነገር ስለተማርኩ ነበር።

ጁዲት በአፃፃፏ ጥቂት ጎረር ያለች እና በግሏ አተያይ በኩል አተኩራ በመፃፍ እምትከራከር ነበረች። የቤትስራውን የሠጠኝ ከመፅሀፏ የወደድኩት አንድ ክፍል ግን ነበር። ኤመርሰንን እንዲሁም የቶከቪል *ዴሞክራሲ ኢን አሜሪካ* እሚለውን መፅሐፍ በ አራትመቶ ገፆቿ ከበታተነች በኋላ፣ የመጨረሻ ምእራፏን ግን ለእማይታወቅ *ሜሪ ኦር ስሌቨሪ ኢን አሜሪካ* ብቻ እሚል ልብወለድ ለፃፈ የቶከቪል ጓደኛ እና የሱን ፅሑፎች ያሳተመለት ፈረንሳይአዊ ጉስታቭ ዲ ቤይሞን እሚሰኝ እማይታወቅ (አንድ መፅሐፍ ብቻ የደረሰ) ደራሲ አድርጋ ነበር። በክብር መታሰቢያነት ያቀረበችው ምእራፏ በመገረም አይቼው ነበር። የ ቶከቪል መፅሐፎችን ሊያሳትምለት የወረሰ እንጂ በራሱ ታዋቂ ያልነበረው ይህን ደራሲ፣ መፅሐፉንም ስስፈልግ በእየቤተመፅሐፎቹ ያዟዟረኝ እማይታወቅ የተጨናነቀ ልብወለድ የፃፈ ግለሰብን በመዝጊያዋ ጁዲት ያለችለት ተገቢነት ግን ነበረው። ይህንን ነበር፦ “ስለ ዘርማንነት እና የሴቶች ሚና በማህበረሰብ ዉስጥ እሚሠብክ ሲሆን፣ የአሜሪካንን መጪ 100 አመቶችም ቀድሞ ያየው ይመስል ነበር። ከቶከቪል እጅግ የማይታወቅ ቢሆንም ከሱ የበለጠ የአሜሪካንን ስነፅሑፍ መንፈስ ግን አጊንቶታል። “እንዴት እዚህ ደረስን/how did we ended up here?” እሚለውን እጅግ ዕዉቅ ጥያቄ አንድቀን ለመጠየቅ ለደፈሩ ማብራሪያ ሊያሰይዝ በቋሚነት የተፃፈ ጦማር አሥመስሎታል። ታሪክም በፍጥነት እየተተወ እሚረሳ በመሆኑ የቀደመው ትዉልድ ፈጠራ እሚዘነጋ ሆኗል።...” ብላ ነበር።

ዳሩ፣ በጠቀሰቻቸው መፅሐፎች ንባቤ፣ እኔ ምንም ተጨማሪ የአሜሪካንን አዲስ ክፍል አላወቅኩም። ግን፣ ጁዲትን የበለጠ ተረዳሁበት። አሜሪካ የወደቀችበትን ዐውዶች እጅግ ከምሯ እንዴት እንደምቶስዳቸው እና ጀግኖቿንም እጅግ እሚማርኳት መሆኗን አወቅኩ።

ዛል ብልም ሱቅ ለመመለስ አሰብኩ። ቆርጬ ካልሰራሁ ሱቁን መነጠቄ ነው። ዳሩ ዛል ስላልኩ ቤቴ ገብቼ አረፍኩ። ከሰዓቱን ሱቅ ገብቼ አመሸሁ። ስመለስም ጠንክሬ ልሰራ ቁርጥ ሀሳቤን ደግሜ አፀናሁ።

በንጋታው ሜይ 6 ላይ፣ ከእጧቱ ጀምሬ ጠንክሬ እና በርትቼ ለመስራት ቆረጥኩ እና በማለዳ ተነሳሁ። ወደ ሱቁ ለመጀመሪያ ጊዜ እንዲያ ባለ በማለዳ ስገባ ግን ደብዳቤ አገኘሁ። ማታ የተተወ መሆን አለበት። ከፍቼ ሳየው የጠበቆች ማሳሠቢያ ነው። የ ሦስት ወሮች ያልከፈልኩት ኪራይ ስላለ የሱቅቤቱን እንድለቅ እሚነግር ነበር። ይገርማል! በቆረጥኩበት ቀን እሚቆርጥ ዜና! የተወዘፈውን እና ባንዴ የተጠቀውን ያክል ብር ደግሞ የለኝም። አቅሜም አይችልም።

የታየኝ ነገር ለኬኔት ደወሎማዋየቱ ነው። እና ረፈድ አድርጌ ኮሎኒያል ደወልኩ። በአስቸጋሪ ስሜቴ እና ምግባሬ ከፍተኛ ቁጣ አደረገብኝ። “ቻልተኛ ስለነበርክ ቀድሞም ያንን ነው የፈለግክው” በእሚል ተናደደብኝ።

ግሳፄውን ለማቋረጥ አንድ ሀሳብ መጣልኝ። የአፍሪቃ አንድ አምባገነን መሪ አነሳሁለት። “የልጆች ፊት ክፍልዎችን፣ አፍንጫ፣ አፍ፣ ጆሮ፣ በመቆራረጥ እሚቦጫጭቅ፤ መልአከዎች እሚያናግሩኝ ናቸው ይል የነበረ፤ አምባገነን መሪ?” አልኩት። ሰሞኑን ስለእሱ ያየሁትን ለመናገር እድል ሆነልኝ።

“አው!” አለ በመገረም። አስቦ በመጨረሻ “ጆሴፍ ኮንዬ! ዩጋንዳ! የ ሎርድስ ሬዚስታንስ አርሚ (ኤልአርኤ)!” አለኝ። አንዳንዴ የድርጅቶችን ስምም ወደኋላ በማንበብ እሚናገረው ሽሙጥ አለ። እየጠበኩ ሳለ አሁንም ቀጠለ። “ኤአርኤል¡” አለኝ። ተሳሥቀን ስልኬን ዘጋሁት። ቀድሞም ጆጆ ጋር መደወል ይሻል ነበር።

እና ከዚህ ሱቅ ልለያይ ነው? እስቲ ልገምግመው። እጅግ ያረጁ፣ ተሸጠው እማያቁ፣ መኖራቸውን ያላወኳቸው ሁሉ እቃዎች ሁሉ አሉኝ ለካ። ይገርማል። እቃዎቼን እያሠስኩ ጊዜ አስረፈድኩ። ቀጥዬ በሩን ልክ ስከፍት፣ አንድ ሽማግሌ ባልናሚስት፣ ወደሱቁ በር ደረሡ እና ሰላም አሉኝ። እንደ እግረኛ ራስ-ጎብኚ *(ቱሪስት)* ሆነው ዲሲ.ን በመጎብኘት እሚንቀሣቀሱ ናቸው። ጥቂት እቃዎች ገዝዝተውኝ ስለከተማው ታሪክ ጠየቁኝ። “መንደሩ እንደእዚህ ወደ ዝቃጭነት ከመፍረሱ በፊት የፐሬዝዳንት አንት እና ሃብታም ወይም ትልልቅ ባለስልጣኖች ብቻ የነበረበት እነበደነበረ አውቃለሁ” አልኳቸው። ጀነራል ጆን ኤ. ሎጋን፣ ታላቅ የአሜሪካ እርስበርስ ጦርነት ጀግና ነበር። “በተለየ፣ የካሮሊና እና ራሌይን ከመቃጠል እና መውደም በማስቀረቱ ትልቅ ሰው ነው እና ሰፈሩ በእሱ ስም ስለከብሩ ተሰይሟል!” አልኳቸው። አመስግነውኝ ወጥተው፣ በድል ፊትእግሮች ወደ ሰማይ የላከች ፈረሱ ላይ ያለውን የሎጋን ሀውልት ከካርታቸው እያስተያዩ ቆዩ። ተመልክተው ሲጨርሱ አብረው ካርታውን አሁንም እያዩ አደባባዩን ከሚያገናኙ መንገዶች የበለጠ ወደ እምወደው ወደ ፒ መንገድ መጓዝ ጀመሩ። ድንገት አንድ ሀሳብ መጣልኝ። ሱቁን ከፍት ትቼው ብርቅስ? ባዶውን ትቼው *ትቶት* እንግዳዎቼን በርቀት ተከተልኳቸው። “ይግቡ ክፍት ነው” እሚለውን

ምልክቱን እንዳንጠለጠለ እና አራት ዶላሮች ያልሞሉ ብሮች በመዳፍብር (ካሽ) መዘገቢያው (ሬጂስተር) ዉስጥ እንደተውኩ አለ። ፒ መንገድ እጅግ ከሁሉ ዉብ የሆነው፣ ወደ ጆርጅታውን እና ዱፖት ሲያደርስ በጣም ቤቱ ሁሉ እየተዋበ እና መንደሩ ገነት እየመሰለ ስለሚሄድ ይስባል። ወደ አስራአራተኛ መንገድ ሲሻገሩ፣ አብሬ ተሻገርኩ። ያኔ እንደመጣሁ ሙብል የቀመስኩበት የቻይና ዶሮቤት፣ ዩም ዛሬ ተዘግቷል። በሱበኩል ሰፈሩን አልፈው ሲያሻቅቡ፣ በሩቅ መከተሌን እየቀጠልኩ የጥቁሮች ሰፈር ደረስን። እዛ አቅም የሌላቸው የተለያዩ የወሲብ ስራዎችን ማታ ይሸጡበት የነበረበት እንደሆነ እሚታወቅ ሰፈር ነው። ስጋቤቶቹም እሚሸጡት ሥጋ ይበሰብስባቸው እና ይሰቃዩ እያወጡም ይጥሉት ሁሉ ነበር። በ አስራስድስተኛ በኩል ነጩን ቤተመንግስት አይተው መጓዝ ቀጠሉ። እኔም መከተሌን አላቆምኩም። በመቀጠል ደግሞ ወደ አስራሰባተኛ ዐዉራመንገድ ወጡ። ሳሙኤል ካፌ አጠገብ፣ ሲደርሡ እጅግ ስለምወደው ጥንዶቹን ብጋብዛቸው ብዬ ተመኘሁ። ሰፈሩ ልዩ ነው። ቆነጃጂት እና ስራፈት ወጣቶች እየተላፉ እሚደሰቱበት ቦታ ነው። ጆሴፍም ይህን አካባቢ ይወደው ነበር። 'ፈረንሳይ ፓሪስ ይመስላል፣ ብቸኛው የ ዲሲ. ከተማ ጤነኛ እና ዘመናዊ ሰፈር ነው' ይል ነበር። አንድ ቀንም ሰክሮ ባመሻሹ፣ የሙብራት እንጨት ተደግፎ እስካርፕ አርጎ አድፍጦ ሲዝናና ይገኘው ነበር።

ጥንዶቹ ሲያልፉት አብሬ እያለፍኩ ነጎድን። ወደ ዱፖ አደባባይ ደረሱ። ያም ምርጥ ዉበት የተጣለበት ነበር እና አድሚራል ዱ ፖን ተመልሶ መጥቶ ቢያየው በስሙ ስለተሰየመ ይኮራበት ነበር። ሎጋን ቢመለስ ግን መንደሩ በመቆሸሹ መከፋቱ አይቀርም። በተለይ ይህኛውን ሰፈር ቢያየው ይህ ንፅት ማለቱ አበሳጭቶ ስለራሱ የበለጠ ያስሠስማዋል። በአካባቢው አረንጓዴ መንደሮች እሚያነቡትን ወጣቶች አልፌ፣ ጎብኚ ጥንዶቹን አሁንም ከእነካርታቸው ሲራመዱ እየተከተልኩ አለፍን። ትንሽ ተጉዘው ግን እከል ገጠማቸው። በአንድ የህዝብ አግዳሚ ወንበር ሲቀመጡ እና ሽማግሌው ሚስቱን እንድትተነፍስ እያበረታታ ሲያነጋግራት የሆነ የጤና እክል እንደተነሳባት ልብእየሳልኩ (ኢማጅን) በልቤ ሰላምታ ሰጥቻቸው ተለየሁ። ወደ ሱቁ አሳቤን መለስኩት። ንብረትን በቀላሉ እንዲህ ክፍቱን ለቅቆ ከመዉጣት እሚያያዘውን ፍልስፍና እሚሰብኩትን ሰዎች፣ በንብረቴ ለመንገደኛ መከፈት ምን ስሜት ቢሰጥ ነው በእሚል እኮንነው ጀመር። ለነገሩ ትቼ የወጣሁት ብዙ ሀብት አይደለም። ተገቢው ስሜት ላይኖረኝ ይችል ይሆን?

## ምእራፍ ሥምንት ፣ ናኦሚ

*ከጁዲት በሥሱ በተሣሳምን በንጋታው፣ ከናኦሚ ጋር ሱቅ ይመጣሉ ብልም፣ ሁለቱም ቀሩ።* እየተጨነኩ፣ የተሣሳምነው ምን ፍች በሷ አለው ብዬ ሳሥብ ቆየሁ። በንጋታውም ተጨንቄ ብውልም፣ ማንም ግን የለም። ተስፋ ቆርጬ፣ "እኔ ከንቱ ድሃ ምንምየለሽ፣ እሷ ትልቅ ሀብታም። አንገናኝም!" አልኩት ለራሴ። "ቤቷ ተጋብዤ የነበረውም፣ ተጋብዤ የበላሁትም ምርጥመብል እና የሀብታም ቤት ዉብ ምሽቱ፤ ሁሉም ተረት ነበር። ወይምደግሞ ቢያንስቢያንስ ከእዛ ከአለፈው በቀረ ምንም ሌላ ወይም ተጨማሪ አይገባኝም።" ልቤ ያንን ብሎ የባይተዋርነት ስሜቴን ወደ ቁጣ ብሎም ቁጣውን ወደ ተሸናፊሀዘን (ፒቲ) ቀየረብኝ።

ኑሮዬን እንደለመድኩት ለመኖር በመጨረሻ ሳሥብ፣ በሦስተኛው ቀን በድንገት ቤቷን ዘግታ ስቶጣ አገኘኋት።ለረዥም ደቂቃዎች ቁልፍ ፍለጋ ስትራወጥ ቆሜ ተመለከትኳት። አተያየቴን አይታው እንድታናግረኝ እያጠመድኳት ነበር። እያየሁ ብጠብቃትም ግን፣ ፀጥ ብላኝ ቁልፏን ስታገኘው በሯንከፍታ ገባች። ተስፋ ቆርጬ ቆየሁ። ንዴቴ ጫፍ ደርሦ እየተበሳጨሁ ከረምሁ። መደዴ ኑሮዬን ማመሡቃቀሌን ትቼ ስራዬን ላጠነክር አሰብሁ። ግን ሱቄም አደጋ ላይ፣ የጁዲትም ሁኔታ እሚያነድደኝ ሆነብኝ።

ልክ በሦስተኛው ቀን ማምሻው ላይ ግን ጁዲት መጥታ ቤቴን አንኳኳች። በርዷት ነበር። በረዶው እያንዘፈዘፋት ተቀምጣ በዝምታ ቆየች። ከእዛ መጠጥ አምጣ አለችኝ። ሲጀመር ስትገባም ሰከር ብላ ነበር። የቆሸሸ የድሀ ቤቴን እንዴት እንዳገኘችው እየጠየቅኩ መጠጡን ቀዳሁ። "አይከፋም!" ስትለኝ ተደሰትኩ።

አጠገብ ላጠገብ ተቀምጠን ስንጨዋወት ልጇን አስተኝታ እንደመጣች ነግራኝ እና ቁልፍ ስትፈልግ ቆሜያየኋት ጊዜ ለምን ፀጥ እንዳልኳት ጠየቀችኝ። ክው አልኩ። የቸኮለች መስሎኝ እንደነበር ዋሽቼ ተናገርኩ። ፈገግ ብላ ተወት አደረገችው እና አዲስ ጨዋታ ዘና ብላ ጀመረች። ዳግ-መቀራረባችንን ወደድኩት። እየተጨዋወትን ቆይቶ ደረቴ ላይ ጋደም ብላ ተኛችበት። ምንም አላዋረዷትም። ዳሩ ምን እያሰበች ይሆን? ጥቂት ቆይታ ነቃች። ለካ አሸልቧት ነሯል። ነቅታ ቆየሁ በእሚል ወዳስተኛቻት ልጇ ለመመለስ በመቻኮል ሆና ተለየችኝ። የቀረ መጠጤን እየጠጣሁ የቀረ ምሽቱን በብቸኛነት አሳለፍኩት።

በንጋታው ኖአሚ ሱቄ መጣች። ለክረምቱ የሁለት ሳምንቶች እረፍቷ በዛ ያሉ ገፆች ካሏቸው መጽሐፎች መርጣ ይዛ ልታነብብ እንደሆነ ነገረችኝ። የመረጠቻቸው መፅሐፎቹን አመጣች እና የቱን እናንብብ ብላ በመጠየቅ አስደመመችኝ።

ናኦሚ መጽሐፍ የመረጠችው የፍዮዶርን ዶይኮቭስኪን *ዘ ብራዘርስ ካማራዞቭ* ሲሆን፣ ለመጡት ሦስት ቀኖች ባለማቋረጥ አነበብብንው። የመጀመሪያው ቀን፣ "አብረን ነው ምናነብበው። ግን አንተ ጀምረው!" በሚል ታስነብበኝ ጀመረች። እንደትልቅ ሰው አጠገቤ ተቀምጣ በጥሞና ስታደምጥ አስገረመችኝ። ተራዬን አንብቤ የተስማማንው ህምሳገፅን ስጨርስ "ቆይ አንድ ገጽ ብቻ!" እያለች ታስጨምረኝ እና ታደምጥ ቀጠለች። አባቴ ተረት መንገር ስለሚወድድ፣ ገፀባህሪዎችንም አግዝፎ እንደእውነት ይቀበላቸው ነበር። እኔም እንደሱ ገፀባህሪዎችን የእውነት አድርጌ መሳሌን ቀጠልኩ። በማንበቡ ስጠመድ ሳትደክም ስትሰማኝ ቆይተን ሲረፍድ፣ "ቤት አሌድም!" በማለቷ ስራ ልፈጥር ተገደድኩኝ። ማፅጃ ሰጠኋት። ቤቱን ፀድቶ በማያቅበት ደረጃ አፅድታ አስደመመችኝ።

ረፍዶ ከሰዓትበኋላ እናቷ መጥታ አየችን። ማንበባችንን እና አዋዋላችንን ነገርናት። ናኦሚ አንዳንዴ እንደምታረገው የሱቄን እቃ እየዞረች ስትጎበኝ ጁዲት ቆም ብላ ጥቂት አጫወተችኝ። "ላንተ ብላ እንጂ ያን የጠጠረ ያዋቂ መፅሐፍ ለግሏ ምታነብ አይደለችም!" አለችኝ።

ከናኦሚ በተደረገልኝ ፍቅር በደንብ ተደነቅኩ። በስልት እንዳነብ አደረገችኝ እንጂ ለራሷ አስባ አልነበረም እና መልሶ በፍቅሯ ኩራት ተሰማኝ። ልቧን በማሸነፌ እና ዋጋ በማግኘቴ ለብ ያለ ስሜት ወረረኝ። እየተጨዋወትን ጥቂት ደቂቃዎች ቆይተን ጁዲት ልጇን ያዘች።

"ነገ የፈለግሽውን ያክል ቆይ፣ አሁን ግን እኒድ" ብላ አለፍላጎቷ አስገድዳ ቤት ወሰደቻት። ይይህ አባባሏ ግን የበለጠ ነካኝ። ማታ ጆጆን ደወልኩለት። ሁኔታውን አማከርኩት።

"ነገ እንዳሻሽ ቆይ ማለቷ አንተን መዉደዷ ሳይሆን አይቀርም። እኔ አስተናጋጅ ሆኜ ብዙ ያሜሪካ ሴቶችን ተመልክቻለሁ። ወዳሃለች ማለት ነው! በርታ ግፋበት።" አለኝ። በቀጣዩ ጧት፣ ናኦሚ የተለመደ የምርአዊነት ተላብሳ ገና ልከፍት ስል አብራኝ ደረሰች። እያጫወተችኝ ትንሽ ቆይተን ሱቄን ከፍተን ልክ ስንማሟቅ ወደ ስራ እንድንገባ አሳሠበችኝ። ሦስት ምእራፎች

አንብበን፣ ጨረስን። ዉሎአችን ገፋ በማለቱ፣ ተቀያሪ አዲስ ሀሳብ አመጣሁ። ከናኦሚ ጋር ሱቁን ማፅዳት መቀጠሉ ይሻላል ብዬ በየንኩ። ሱቁን በአጋጣሚው በደንብ ላፀዳዳው አስቤ የጥገና ስራ ሁሉ እየከወንን ወረድንበት። በመጨረሻ በደንብ እያማረበት መጣ። ቀናቸው ያረጁ እቃዎች ተጣሉ፣ የተነቃቀሉትን ዕቃመያዣዎች ሁሉ ገጣጠምኩ። ሁሉም አማረበት። ቸኮሌት ሽልሜያት ወዲያው ተደስታ በላችው። ቤት እምትወስደው ከረሜላ ደግሞ ስሠጣት በኪሷ ሻጠችው።

ጁዲት አመሻሽታ ሻይ ይዛ መጣች። “ልናነብብ ከሆነ ሻይ ብንጠጣ ምንአለበት” ብዬ ነው አለች። “እኛ” በማለቷ ተደምሜ ለዮሴፍ ወሬውን ቀጥዬ ልናገር ቋመጥኩ። እየጠጣን፣ ጁዲት እና እኔ በየተራ ለግማሽ ሰአት አነበብን። ናኦሚም እየጠጣች አድማጭነቷን ማስመሠል ቀጥላ ቆየች። ድንገት የማልፈልገውን ነገር ከወንኩ። ዙሪያችንን መህምገም ጀመርኩ። ብቻ ቶሎ ግን ወደ ሁኔታውን ተቀብሎ መደሠቱ ተመለስኩ።

“ከእዚህ በላይ በሆንን ብዬ ከእምመኝ፣ ብልህ ከሆንኩ፣ ይህ የግማሽሰአት ቆይታዬ በቂው ነው። እና በእዚህ ልርካ! ይሄ ትልቅ ነው! በቃኝ ብዬ ልረካ ይገባኛል!” ብዬ አሰብኩ። በሱቁ ወደፈጠርነው ወደድባባችን እየተደሰትኩ ተመለስኩ።

**<u>ምእራፍ ዘጠኝ ፣ ባዶ ሱቁ እና ጋሼ ብርሀኔ፣ ካፒቶል ግሪል እና የጁዲት እና ናኦሚ ዉበት</u>**

*ከሱቅ ወጥቶቼ አዛውንት ጥንዶቹን ከመሬት ተነስቼ እየተከተልኩ፣ በ ዱፖ ሰርክል እንዳለን ትልቅ ባለስልጣን በአጀብ ሲያልፍ አየሁ።* የሊሞዚኑ ተጓዥ እና የመኪና ጥበቃ ሽርጉድ ወከባው፣ ከሰርክሉ አካባቢ ከነበረው ድሀ ህዝብ የተመልካችነት ሚና አንፃር እየገረመ ተነፃጸረብኝ። ልዩነቶቹን ታዘብኩ እንጂ አዲስአበባም የንጉሡም ጊዜ ያው ነበር። ንጉሡ ካለፈ መንገዱን ፅድት ያደርጉት ነበር። ወታደሮች ሰአት ቀደም ብለው በመገኘት ለማኝ፣ አንካሳ፣ ቆሻሻ ያፀዳሉ። ታማኞች በእየመንገዱ ዳር ይፈስሣሉ። ልክ ንጉሱ ሲያልፍ እየሰገዱ ያሳልፉታል። እዚህም ሁሉም እየተቁለጨለጨ ባለስልጣኑን እየተመለከቱ ሳነፃጽር ቆይቼ ሀሳቤን አጠለልኩ። መልክአ-ልዩነቱን ማስተዋሌን ትቼ ወዲያው ዞር በማለት አንድ የሳንቲም ስልክ ዘንድ ቀረብኩ። አጎቴ ብርሀኔ ጋር ደወልኩ። “ሱቄን በብድር ይታደጋት ይሆን? ምን አለው ብዬ ደግሞ ልጠይቀው ነው!” አመነታሁ። ግን ዘገየሁ። ስልኩ ጠራ። አላነሳም። 'መልእክት ይተዉ' እሚል መልስ ተቀድቶ ስላገኘሁ፣ 'እመጣለሁ' እሚል መልእክት ለመተው ድጋሚ ጨከን አልኩ እና አሰብኩ። ድንገት ቤቴ ሳልደርስ አጎቴ ቤቱ ገብቶ መልእክቱን ሲሠማው ደረሰአልደረሰ ብሎ ከእሚጨነቅ ባልተነፍስ ይሻለኛል። አሰብ አድርጌ ስልኩን ያለመልእክት-በመተው ዘግቼ፣ አማራጭ አሰብኩ። ወደ ዮሴፍ ጋር ደወልኩ። ኮሎኒያል ግሪል ሬስቶራንት አስተናጋጅ አንስታ አገናኚኝ ስል አቅማማች። ዘጋሁት እና ከወጣሁ ሁለት ሰዓቶች ወደአለፈበት “ባዶው” ሱቄ ደወልኩ። ኬኔት ሁለቴ እንደደወለ መልእክት ሳጥኔ ነገረኝ። ዘግቼው በሌላ ስሙኒ ኬኔትን ደውዬ መጀመሪያ በጨዋታ ለመጀመር ስለ ቫለንቲን ስትሬሰር ልጠይቀው አሰብኩ። በታሪክ እሱ በእድሜ ትንሹ ግልበጣ የከወነ አፍሪቃአዊ ነው። በ25 ዓመቱ የአለምም ወጣቱ መሪ ነበር። ኬኔት ጋር ሲጠራ ይህ የቅርብ ትውስታ ጨዋታ አይደለም ብዬ ዘጋሁት እና ሱቄ ደወልኩ። ስልኬ ተነሳ። ተገረምኩ። ድምፁ የሚስስ ዴቪስ ነበር። ከጀርባ የልጆች እሚንጫጫ ድምፅ ቢኖር እና ዕቃዎቼ ከስረውብኝ ሊሆን ቢችልም ተደስቼ “ኡፍ!” ብዬ ስልኩን ዘጋሁት። ወደ አጎቴ ለመሄድ በባቡር ተሳፈርኩ። ከሁሉ የድሀዎች በሆነው የሜሪላንድ ዳርቻ እሚኖረው አጎቴን ለማወያየት ቆርጫለሁ።

ባቡሩን ስይዝ፣ የ *ቨርጂኒያ ኮሚኒቲ ትምህርትቤት* ማስታወቂያን በባቡር ዉስጡ ተለጥፎ ተመልክቼ ተገረምኩ።የተማርኩበት ትምህርትቤት ስለነበር ማስታወቂያው በይዘቱ እምብዛም ባለመለወጡ እጅግ ተደነቅኩ። አንድ ነጭ፣ አንድ ሂስፓኒክ፣ አንድ ኤዢያአዊ፣ እና አንድ አፍሪቃአዊ በጠቅላላው አራት ተማሪዎች በደስታ በአረንጓዴ ሳር ተቀምጠው ይታይ ነበር። ማስታወቂያው እንጂ እዉነቱ እምብዛም ነው። ጆጆ ብቻ እየተደበቀ እሚገባበት እንደሆነ እና በምርጥ ማስታወቂያ የበረቱ እንደሆኑ አሉ። ለጉዞ እማይደላው ባቡሬ ግማሽ ሰዓት ቀድማ ከዋናዋ ዲሲ. አመለጠች። ትልቅ የአሜሪካ ከተማዎች መሀከል እንዳቶን ያ አድርጓት ነዋሪዎቿ ታእታይአዊ ብሶት (ኢንፈሪዮሪቲ ኮምፕሌክስ) የጨበጣቸው ናቸው። ቀጥላ ባቡሯ ወደ አጎቴ ቤት ተዳረስን። ሲልቨር ሮክ ኮምፕሌሥ አካባቢ ያለው መንገዱ የተራቆተ፣ አስቸጋሪ እና ቸላ የተባለ የድሃዎች መኖሪያነትን በገሀድ እሚያስመለክት ነበር። ላብ አልቦኝ በሃያስምንት ፎቆች አፓርትመንቱ ዉስጥ የአጎቴ ወለል ላይ ለመሄድረስ ወደ ህንፃው ዘለቅኩ። ስገባ ግን፣ ለአጎቴ እምለውን ነገር እሥል ነበር። “ሀሳቤ ሱቁን ለመሸጥ ነው!” ብለው ‘ህይወትህ መሻሻል ሊጀምር ነው' ብሎ እሚያስብ እንደሆነ በመገመት ሱቅ የመሸጡን ሀሳብ ልነግረው ወሰንኩ። ሢደሰት እና መልካም ሲሠማ ሁሌ እንደሚያደርገው አምላክን ላስመሰግነው ነው ማለት ነው።

ከደርግ ሽሽት ከኢትዮጵያ ወተው በአፓርትመንቱ የደረሱት ሀበሻዎች ኑሮዬን እንደ አዲስአበባ ቅጥያ አድርገውት ስለነበር ደብሮኝ በአንድ ምክንያትነት ወስጄው መዉጣቴ ልክ ነበር። አሁንም አማርኛ እንጂ እንግሊዝኛ ማውራት እና ማድመጥ እንኳ አልገጠመኝም ነበር።

አሁንም ሌላዎቹ ተበላሽተው የእሚሠራው የነበረው አሳንሡር ላይ ብዙዎች ታጨቅን። የአማርኛ ወሬ እና ጨዋታው ተፋፋመ። አለመካፈል ራስወዳድነት ነው እሚሆነው። ቀልድም ሲነገር ሰማሁ። “አሳንሣር ሙሉ ኢትዮጵያአዊ ምን ይባላል? መልስ፡- ሊኖር አይችልም!” ተሳቀ። እኔም ሳቅኩ። ሌላም ቀልድ ሌላዋ አከለች። “ስንት ኢትዮጵያአዊ አሳንሡር ዉስጥ ማጨቅ ይቻላል? መልስ፡- ሀገሩን በሙሉ!” ሁሉም ተሳሳቀ። ወዲያው አንዳንዶች እየወረዱ ወደላይ ስናሻቅብ ምርአዊ (ሲሪየስ) ወሬዎች ጀመሩ። “ያቶ ንጋቱ ልጅ ገና ወፍጭጭ ሳይል ለብቻዋ ታክሲ ይዛ ስቶጣ ታየች አሉ!” “ትሽ! ምን ነክቶናል!” “እከሊት ደግሞ ሰርቃ ተገኘች ሲሉ አልሰማሁም መሰለሽ! ዝምበይ አትናገሪ ደሞ!” “አይ! ሀበሻነት እና በሂደት መጥፋቱ አይቀሬ ነው። ሁሉ ደግሞ አሜሪካን የተሻለ እየተቀበለ ነው አሁን አሁንስ! አይ ኢትዮጵያዊነት! እይ!” “ጠ!” ወሬ ሳልካፈል ሁሉን እየሰማሁ ቆየን እና ወለሌ ስደርስ ወረድኩ።

አጎቴ ክፍል ስደርስ፣ አብረን ስለኖርን የራሴ ቁልፍ ቢኖረኝም፣ ከወጣሁ ስለቆየ ሰተት ብዬ ልገባ አይገባም በማለት አንኳኳሁ። ጋሼ ብርሀነ ሥላሴ የለም። ከፍቼ ገባሁ። ቤቱ በፊት ሲኖርበት እንደነበረው ነበር። ገፅታውን ለመቀየር ቢዝትም አልተሳካለትም ማለት ነው። የሚጠቀማቸው ወንበሮችን እንኳ እቀይራለሁ እንዳለ ብቻ ይኸው ዛሬ ያለምንም ዝግመት ደረሠ። እኔ እራሱ እተኛበት የነበረው ሶፋ እንዳልተነካ አለ። አጎቴ እጅግ እቃ እሚንከባከብ እና እኔንም እሚወድድ፣ እሚንከባከብ መሆኑ ዛሬም ግልጥ ነው።

ብርሀኔ ብዙ ገንዘብ ዛሬም የሌለው ሲሆን፣ ከገቢው ኩርማኑን ፈንክቶ ሀገርቤት ሲልክ የቀረው በመጠኑ በድህነት ሂሳብ ዛሬም ጭምር ያኖረዋል። አሁን እኔን መደገፍ እና ሱቁን ማዳን መቼም አይቻለውም። በተስፋ መቁረጥ ሳለሁ ኬኔት ታወሰኝ። የሆነነገር ማድረግ አቅቶኝ 'ዘገየሁ' ማለት ነው። ትንሽ መፀፀት ግድ ይለኛል።

ከወጣሁ አምስት ሰዓት ወደሆነው ክፍት የለቀኩት ሱቄ ዳግ-ስደውል ያረጀ ሰው አነሳው። ከጀርባው ወጣተ ሴት በድምፅ ትሰማ ነበረች። ዘግቼው በሀሳብ ከመዋጥ ብዬ የአጎቴን ደብዳቤዎቹ ጎን ያለውን ብር ማጠራቀሚያውን ፈተሽኩ። አንድሺህ ዶላሮች አገኘሁ። “ልስረቀው?”

“ሠርቄው ደብዳቤ ብተውለትስ?” ከራሴ ተወያየሁ። አንድሺህ ዶላሮቹ የሱቁን ኪራይ ልከፍል ወይም እናት እና ወንድሜ ጋር ልሄድ ቲኬት ልቆርጥበት ያስችለኛል። መልሼ ግን “ብከተው እና እንደደረስኩ ሳይታወቅ ቶሎ ብመልሥስ?” ብዬ አሥብኩ። አንጡራሀብቱ እንደሚመሰክረው ምን ሀያታት (ቱ ዲኬድስ) እዚህ ቢኖርም፣ ብርሀኑሥላሴ ግን አሜሪካአዊ አይደለም። የዲሲ. ድህመንደር አንድ የአፓርትመንታቸው ቋሚ ነዋሪ ብቻ ነው። አሜሪካአዊ መሆንም አይችልምም። እስኪሞትም ኢትዮጵያአዊ ነው። ልቡ ዉስጥ ኢትዮጵያ ብቻ ናት ያለችው። ቤቱ ያለው የደብዳቤ መዓት ቢጨምርም የሀገረ ኢትዮጵያ ጉዳይ ምንም ሳይለወጥለት ግን አለ። እሱም እስኪሞት ሀገር ናፍቆ እሚሞት ይሆናል። በእጄ እማጨማልቀው አንድሺህ ዶላር ትኩረቴን መልሶ አመጣው። “ከሱ ከምሰርቅስ” አልኩኝ። “አጎቴ ሳይመጣ መምጣቴንም ሳያቅ ልመለስለት እንጂ አንጡራ የስንት አመት ሀብቱን ይኸ ከሆነ በህግአዊ መንገድ እራሱ ተበድሬም እንኳ ለመጋራት መቆየት የለብኝም!” ብዬ ወሰንኩ። ደብዛዬን ከመንደሩ ላጠፋ ተጣደፍኩ።

ወደስራው ቦታ በአካል ካልመጣህ ወደእሚለኝ ጆሴፍ ጋር ለመሄድ፣ በባስ ልሳፈር ብዬ ቶሎ ከአጎቴቤት ወጣሁ። በባሱ ተሳፋሪዎች ጭንቅንቅ በማለቱ፣ መተንፈሻ እንኳ ባለመኖሩ፣ እጅግ እወደው የነበረውን ደርግ ወንጀል የፈፀመበትን የአዲስአበባ ባስ አስታወሰኝ።

ጆሴፍ በኮሎኔል ግሪል አስተናጋጅነቱ፣ በግልፅ ባይናገረውም፣ የእሚኮራበት ስራው ነው። የስራውን ስፍራ ሲገልፁ የሚለው፣ ‘የትልልቆች መብልቤት ነው!’ ‘የልሂቃኖች (ኤሊትስ) መመላለሻ ደጅ ነው!’ እሚሉ አድናቆቶችን ነው። ያ ማለት በስራው ይኮራል ማለት ነው ብዬ አምናለሁ። ሴናተሮች፣ ጠበቆች፣ ሎቢስቶች ወዘተ. ምሳ እና ራት እሚበሉበት ሲሆን፣ ጆጆ የመቶ ሴናተሮቹን፣ የተወካዮች ም/ቤት ደግሞ ግማሾቹን ያውቃቸዋል፣ ፊታቸውን ለምዶታል። ሁሌ ይገመግመዋል። በሳምንቱማብቂያ ቀኖች በተገናኙ ቁጥር የፊትአቸውን ሁኔታ ለሁለቱ ጓደኞቹ ይተነትነዋል። የፖለቲከኛዎቹን ፊት ካወቀ እና ከገመገመ፣ ፖለቲካውን በደንብ አጠናቅቆ የተረዳ ይመስለዋል። ፊትአቸውን ካወቀ በኋላ ግን ከፊታቸው ጀርባ ያላቸውን የፍሬነገር ነጥብዎች አይመለከተውም። መጀመሪያ ወደ ዲሢ. ሲመጣ፣ እንደ ባስቦይ፣ ቀጥሎ የሆቴል እንግዳ ተንከባካቢ (ቤልሆፐ)፣ ቀጥሎ አሁንደግሞ እንደአስተናጋጅነት እየሠራ ነው። በሥራው ተስፋ ሳይቆርጥ ሦስተኛ ተከታታይ ዲግሪዎች ሊሠበስብ እና ዶክተር (ሊቀምሁርዎች) ሊሆን ሁሌም እንዳሠበ ቆይቶ ነበር።

በቅርቡ ግን እጅወደላይ ማለት ሊጀምር ይመስላል። ተስፋ በመቁረጥ ዘረሁኔታ (ሞድ) እየገባ ሲሆን “በከተማው ቤተመፅሐፍቶች በበቂ ተደራሽነት ስላለ ከፍሎ መማሩ አያስፈልግም። በግል መማር ይቻላል!” ሲል ሰምቼዋለሁ። ይህ አነስ ያለ የእጅመስጠቱ ምልክት ነው።

አንዴ በታዳጊነቱ ሀገሩ ሳለ ያነበበው አንድ ግጥም፣ ናፈቀው እና አግዙኝ ብሎ በእየመፅሐፍቤቶች አፈላልገን አገኘንው። ግጥሙ ስለኮንን ሲሆን፣ ድህረ-ነፃነት በስልሳዎቹ ተስፋ መጥፋቱን ከዳንቴ አሊጌሪ ዲቫይን ኮሜዲ አገናኝቶ የጠቆመ ነበር። ግን ያ ግጥም ከዳንቴ ይለያል። ዳንቴ የተረከው፣ ከሲኦል ሲወጣ ገነትን እያየ ስለነበር በቀናአዊ አጨራረሥ ነበር። ይህኛው ግን አጨራረሡ መልካም አምነበረም።

ጆጆ በሂደት በአስተናጋጅነቱ አመቶች፣ በካፒቶል ሆቴል እና በኮሎኒያል ግሪልም፣ ግጥምን እራሱ እያስተካከለ መፃፉም ሰለቸው። ቤቱ ሲገባ ግጥም ላይ አቀርቅሮ ይገኝ ነበር። በቅርቡ፣ እንዲያውም የግጥም ነገሮች ሰልችቶት ቤቱ ሲገባ በባዶ ቤቱ ባለው ወንበር ላይ ተቀምጦ እየጠጣ እና እያጨሰ ይገኛል። በመናቅ ስሜት ሆኖ የተስተናጋጆቹን እረባሽነት እና አስተናጋጆቹ ተናድደው እንዲወጡ ያልሞከሩት እንዳልነበር መጠጥ ፉት እያለ በሌላ እጁ ሲጋራ ጨብጦ በንቀት ስሜት ያወራል። ኮሎኒያል ግሪል ማለቱን ትቶ በግልጥ ኮሎኒያል ብቻ ይለውም ጀመረ።

ወደ ስራቦታው ስደርስ፣ ተቀብሎ አስቀመጠኝ። ግን ብዙ ሳንቆይ ለማስተናገድ ብሎ ጆይ በእየወንበሩ ሲሯሯጥ፣ ልቡ ተነክቶ አዘነ። እንድመጣ ቢወተውትም፣ ጓደኞቹ በስራሰዓት ሲጠመድ እንዳይመጡበት ይሻ እንደነበር ግን ተረዳሁ። አሁንም፣

በአስተናጋጅነት መቅረቱን እማይበት እየመሰለው ሲያስተናግድ አፈር እያለ እየተመለከተኝ ነበር። እሱ እንዳዘነው የኔም ልብ ለሱ አዘነለት። እየተጨናነቀ ነጭ ሦስት እናቶችን እያሳሳቀ አስተናግዶ አየት ሲያረገኝ ሀፍረት ወረረው። ሁኔታውን ተረድቼ አኳኋኑ አላምር አለኝ። ሊያስተናግድ ወደ ኩሽና ሲዘልቅ ለመውጣት አሰብኩ። ልክ ሲመቻች፣ በልቤ “ቻው” ብዬ ወደ መንደሬ አዘገምኩ። ሰፈሬ ከኮሎኒያል ግሪል ሀያ ብሎክዎች ነበሩ። መንደርዎቹ፣ ከቶ በረዥም ጊዜ ያልተቀየሩ፣ ሌላው ሲመነደግ የቀነጨሩ ነበሩ።

ወደተውኩት ሱቄ እየተመለስኩ ብዙ የከፉ ነገርዎች ይገጥሙኝ እና ይዘረፍ ወይም ይቃጠሉ እንደሆነ ሳልኩ። አጎቴም ሆነ ጓደኛዬ እሚረዱኝ አየደደሉም። “አድነው ይሆን ወይስ ይለየኝ?” ከራሴ እየተወያየሁ ተወት አድርጌው አካባቢውን እቃኝ ጀመር። እስከ እኔ ሰፈር ያለው ያልተለወጠ መንደር ዉስጥ ለመኖር በቋሚነት መወሠኔን በከፍተኛ ዳግ-አስብ ጀመርኩ። የመጀመሪያዎቹ ሁለት አመትዎቹ እጅግ የአዲስአበባ ብጤ ሆኖልኝ ነበር። ብዙ ቤተሠብዎቼንም አናግር፣ እጨዋወትም ነበር። ሌላ ያልበለፀገ መንደር ስመለከትም አዲስአበባን አቻ አድርጌ አስብ ነበር። በተለየ፣ አባቴን ማሥታወሥ እና በሀሳቤ እሱን ማውጋት ትልቁ ሀገሬን ማሰቢያው መንገዴ ነበር። ከቤት መራቄን መልመዴ አባቴ ከሀሳቡ ከመራቁ የተከተለ ነው። “ሁሉም ከአንተ ጋር አብሮ ሄደብኝ አባባ!”

**<u>ምእራፍ አስር ፦ ጁዲት እና የገና መዓቱ</u>**

*ማምሻውን ጁዲት አምጥታ ሻይ በጠጣንበት ማግስት፣ በጊዜ ሱቄን ከፈትኩ። በጧት ጁዲት መጥታ እራት እማቅደው ካለ ጠይቃ የለኝም ስል፣ መልካም ዉሎ ተመኝታልኝ ተለያየን። ማምሻውን፣ ተመልሣ አብስላ ወደ ሱቁ ከናኦሚ ጋር መጣች።* ምሽቱ ሳይቀዘቅዝ በጊዜ ሱቄን ዘግቼ እንድንመገብ ቦታውን አመቻቸሁ። እየተጨዋወትን በላን እና ወደ ሞል በጁዲት መኪና እንድናቀና የዕቅዷን ሀሳብ አቀረበች። ገና እየተቃረበ ስለሆነ ሽርጉድ በእየሰፈሩ ይታያል። ተጉዘን ብሔራዊውን የገና ዛፉን ጎበኘን። ናኦሚን እንዳቅፋት ጁዲት ሀሳብ አመጣች እና አቅፌ ዛፉን የበለጠ እንደኛ እንድትዝናናበት አደረግኩኝ።

ከመልካም ቆይታ ጀርባ፣ ወደ ሰፈር ስንመለስ "ቤታችን ያለውን ገናዛፍ ካላየህ!" እያለች ናኦሚ፣ ደጋግማ ጠየቀችኝ። ጁዲት "ሻይ ጠጣ እና ትተኛለህ።" ብላኝ ግብዣ ደመረች። ወደእነሱ ቤት ጎራአልኩኝ።

ገና ስገባ፣ ናኦሚ ከፊልየጠፋ አባቷ እና የቀድሞው የጁዲት ባል፣ ከጀርመን የላከላትን ስጦታ አሣየችኝ። አደነቅኩላት።

በአለቅጥዉድ ስጦታዎች እና ገናዛፍ ጁዲት ቤቱን ለልጇ አስጊጣ አስጎበኘችኝ። ለናኦ የገዛቻቸውን ስጦታዎችን ተደብቀን በማሸግ እያዘጋጀን ሳለ በወሬያችን መሀል "ተለቅ ያለ ነገር እወዳለሁ" ስትል "እኔ ደግሞ እርካሽ እና አነስ ያለ ስጦታ እወድድአለሁ" አልኳት "የተሳሳተ ቤተሰብ ነው የመረጥከው" አለችኝ። ከው አልኩ። ሳታስብበት ያለችም ይመስል ደንገጥ አለች እሷም። እስካሁን የጥቁር ባሏ ምትክ ነበር አድርጋ ያሠበችኝ ማለት ነው? ሴቶች እሚወዱት ጠየም ያለ፣ የተማረ፣ ሊቅ፣ ግለትምምንአማ፣ አፍሪቃአዊ፣ እንደነበር ያን ባሏን ሳልኩት።

"እኔ ላይ የሱን ምትክ ፈልጋ ከሆነ ተሳስታለች!" ብዬ ሻዩን ሳልጠጣ ገና ተናድጄ፣ ለመሄድ እንዳሠብኩ አሳወኳት። በንፁህ ማንነቴ እንደሆንኩት አለመወደዴን እና በመልኬ መገመቴን በመጥላት፣ ተስፋ አልታይህ አለኝ። "ሁሌ እራሴን በመስታወት እያየሁ ከእሷ ራሴን ማወዳደር የለብኝም፣ ያን ባደርግ እንኳ አንዴ አንድ ነገር ልክ እንዳሁኑ ሲፈጠር ሮጣ ለቤተሰቤ አቶንም" ብትለኝ የነገሩ ማብቂያ ይሆናል" ከራሴ ተወያየሁ። ነገረሁኔታው ተረባበሸኝ። ለመሄድ ተነሳሁ። ዳግ-ደንግጣ፣ "ቆይ!" ስትል "እንቢ መሽ" በማለት ቸክ አልኩ። ተስማምታ ትሸኘኝ ጀመረች። "እንደወትሮው ትስመኝ ወይስ በምን እንለያይ ይሆን?" እያልኩ ከፎቁ ተረማምደን በዝምታ ወረድን። በሯ ላይ ስደርሥ ጨብጣኝ ብቻ ሸኘችኝ።

ተናድጄ ክስል አልኩኝ። ከቤቷ ወጥቼ በአደባባዩ ዙሪያ ባለው አንድ አግዳሚ ላይ በቀዝቃዛው አየር ተቀመጥኩ። ሴተኛአዳሪዎች እሚወጡበት ሰአት ነበር። ለነገሩ ወደሱቄ ከሚመጡት ሴተኛአዳሪዎች ሁሉ እተኛ ነበር። ሊገዙኝ ሲመጡ "ማታ ተመለሱ እና በነፃ ግዙ" በማለት እሸኛቸው ነበር። አመሻሽተው ሲመለሱ ለግማሽ ሰአት ያክል በአካሌ አጨዋውቼ የፈለጉትን ደግሞ በነፃ በመሸጥ እሸኛቸው ነበር። አሁንም አንዷ ቅሬ "የምትፈልገው ካለ!" ብላ ከጨለማው መልእክት ላላከችልኝ። "ቤትገብ ነኝ" ብዬ በመመለስ ወደቤቴ አዘገምኩ።

ምሽቱን እና ሌቱን እየቃዠሁ አድሬ ሲነጋም ሱቅ መሄድ ቀርቶ መነሳት ደበረኝ። ቀረሁ። ቤቴው ዋልኩ። መሸ። በእዛው ለመተኛት ስጣጣር ደግሞ ነጋ። አዲስ ጠዋት። ዘግየት ብሎ ሱቅ መክፈት እሚለው ሀሳብ አሸነፈኝ። ወደሱቄ ሳዘግም ናኦሚን ሱቁበር ላይ ስትጠብቀኝ አገኘኋት። እጅበደረት አድርጋ የመካሪነት ስሜት ተላብሳ፣ ትላንት በመቅረቴ ማዘኗን ገለጠችልኝ። "ይቅርታ" ብዬ በሬን ከፈትኩ። ገብተን መፅሐፍአችንን ስናነነብቡ አረፈድን። ከሰአት በኋላ ደግሞ አዲስ ነገር ዉስጥ ልጠምዳት አሰብኩኝ። የገናዛፍ ታወሰኝ። አንድ ለሱቁ ማበጀቱን ተያያዝነው። ስንጨርስ አልሸጥ ያሉትን ወረቀት እና መሳያዎችን ሠጥቻት ባክነው ሳይቀሩ እንዲያገለግሉ አደረግን። እና የተለያዩ ስእሎችን ዛፉን ለማሽብረቂያዎች አድርጋ ሳለችልኝ። ቤቱን እጅግ አስዉበን ስንጨርስ እንዝናናበት ጀመርን። ተዝናንተው፣ ጥቂት ስጦታ ላዘጋጅ አስቤ በግሌ ተፍተፍ አልኩ። በመጨረሻ ለእናቷ የይቅርታ ደብዳቤ አስይዤ ላኳት። የገና ስጦታ ለመግዛት ሳስብ አዲስ ባህል የማዳበር እና አሜሪካአዊ የመሆኑ ነገር እየጠጠረብኝ መምጣቱን አስተዋልኩ። ህይወትን በእዛ መንገድ መልመዱ እየበዛ መምጣቱ ነው በእሚል አለፍኩት። የሀገርቤት ኑሮን መዘንጋቱ እየተቋቋመብኝ ነው። በፊት ለገና በያመቱ እደውል ነበረ። አሁንአሁን ግን የሀበሻ ቀንመቁጠሪያን እየረሣሁ መጣሁ። እናቴ ግን ብትቆጣም፣ ወንድሜም ጭምር ከዓይኔ እየራቁ እንደ እንግዳ እየሆኑብኝ ሄዱ። ለአደጋ ያጠራቀምኩት ሁለትመቶ ዶላሮችን አንስቼ ማውጠንጠን ጀመርኩ። ምን ልሸምት? ለናኦሚ የጠፋ አባቷ ከላከላት የተሻለ፣ ለጁዲት ርካሽ እና ትንሽ ስጦታ እወዳለሁ ሲላት እንደተጣሉበት የምወደው ከበድ እና ከበር ያለ ነገር ስላለችው ያንን መሰል ነገር፣ ለዳዊት ቀደም ሲል መሆን የነበረበትን ደግ ወንድም ሊሆንለት፣ ለእናቱ "መቼም የተማመኘብኝን!" መልእክት እና ካርድ ለማዘጋጀት እና መስጠት አሠብኩ። በበዓሉ ልደሰት እናም ላስደስት ቆርጬ በ ፒ ጎዳና ወደ ጆርጅታውን ሞል ይህን ሁሉ ልሸምት አዘገምኩ።

ዞርኩ፣ ተዟዟርኩ። ለወንድሜ ነጭ የቲሸርት ልብስ፣ ለእናቴ እምቶደውን ሽቶ ሸመትኩ። ለጁዲት ደግሞ እምቶደውን ተለቅ እና ወሰብሰብ ያለ ነገር ለመፈለግ ማውጠንጠን ያዝኩ። ያ፣ መፅሐፏ እና ፍልስፍናዋ ታወሡኝ። የሆነ የአሜሪካንን መፅሐፍ ጠጠር አድርጎ እሚገልፅ ግጥምአዊነትም የተላበሰ መፅሐፍ ልገዛላት አሰብኩኝ። እንደ እምትወደው ባለመጠራጠር፣ ታሪክ እና ፓለቲካን ግጥምአዊ አድርጎ እሚያወራ መፅሐፍ ልገዛላት አሠብኩ።

ገና ባለዕዳ ብሆንም እና ብር ባይኖረኝም፣ የጋዝ እና ሙብራት ክፍያዎቼን ተጠቅሜ እንደበዓሉ ግርማ ዝንብ እምትወደውን የኤምሊ ዲከርሰንን ግጥምዎችን ከአንድ ያረጁ-መፅሐፍዎች መደብር ገዝቼ ያዝኩ። ለናኦሚ ደግሞ በአስራአንድ አመቶቿ ካለቅጥ ቀድማ እንዳደገችው የበለጠ ደግሞ እሚያሳድጋትን ስጦታ አስቤ አስቤ፣ ማስታወሻ መዘገቢያ ልዩደብተር (ዳያሪቡክ) ገዛሁላት። ሥጦታዎቼን ሰብሥቤ ስለጨረስኩ ካፌ ተቀምጬ የናኦሚ ማስታወሻ ላይ መልእክቴን አለማሁ። *'ለምድር ብልኳ የአስራአንደአመት ልጅ፣ የኢድሜዘመኗን ምስጢር እንድትፅፍበት የተሰጠ'* እሚል አውጥቼአውርጄ ካገኘሁት ሁሉ መርጬ ፃፍኩ። እምቴድበት ይዛው ተዘዋውራ ብዙ ድንቅ ሀሳቦቿን ሁሉ እንድትፅፍበት አቀድኩላት።

ስጦታዎቼን ሸክፌ ቤቴ ስደርስ ግን፣ ጁዲት የተወችው ደብዳቤ አገኘኝ። *'ዉድ እስጢፋኖስ፣ ስላስታወስከኝ እና ደብዳቤ ስለላክልኝ አመሰግንንህ አለሁ። ወደ ኮኔክቲከት እህቴ ጋር ለበአሉ ሄደናል። ስንመለስ እንደምንገናኝ ተስፋ አለኝ። እስከንመጣ ይቅርታ። መልካም በአል ይሁንልህ!'* እሚል መልእክት ትታልኝ አገኘሁ። ቀዝቃዛ ስሜት ገጨኝ።

ለብቻዬ ስጦታዎቼን ብዙጊዜ ወስጄ ስጠቀልል ቆይቼ፣ ሲመሽ ለግል አፍታች እርምጃዎቼ ወጣሁ። ጥቂት ተራምጄ በአቅራቢያ ካለው መናፈሻ ደርሼ ሳለ፣ አንዲት ሴት የገና የፍቅርቀጠሮ (ዴት) ከፈለግኩ ስትጠይቀኝ ተቀብዬ ቤቴ ይዣት ሄድኩ። አብረን በአንድነት አደርን።

በማለዳ ተነስታ ተለይታኝ ስትወጣ አንድ ስጦታ ልሰጣት አሰብኩ። ለወንድሜ ከገዛሁት እማይሆናት ቲሸርተደ ስጦታ በቀረ ካሉት ስጦታዎች ዘርግቼ፣ አንድ ዉሰጅ አልኳት። አቅማምታ አንዱን መረጠች። ሽቶው ነበር። ነግሬያት የመረጠችው ሽቶነቱን ስታውቅ ግን "እኔ አልጠቀምም ለምታውቀው እና እምቶደው ስጠው" ብላ ተለየችኝ።

በገና ማለዳ፣ ብቻዬን ሆንኩ። ስደተኛ በበዓልም አገልጋይ ነው እሚል ሀሳብ ያዘኝ። እንጂ አንድ ሰው ወይም ቤተሰብ ጋር ለማክበር እገኝ ነበር። ስለእዚህ ስደተኛ እሚያከብረው በዓል አደለም በእሚል ሡቅ ልከፍት እና ላገለግል ተነሳሁ። በብቸኝነት ተደብሬ ስነግድ፣ አሙቱን ሙሉ ሊራራቅ ይጣጣር የነበረን ለበአል ግን የተሠበሰበ ቤተሰብን እቃ እየቸረቸርኩ አገለገልኩ። በተለይ አሉሚነም-ፎይልን ከግማሽአመት ሽያጬ የበለጠ ያን ቀን ተሸጠልኝ።

ለዓይንሲይዝ፣ ጆይ ጋር ደወልኩኝ። "ኬኔት ለብቻው በበዓል ሥራ ሊሠራ እና ቢሮውን ለማስተዳደር ሊቀበል እንደታመነ በአለቃው ተነግሮት፣ ለብቻው ሥራ ገባ!" ብሎ ነገረኝ። የምፀቱን ድምፅ ቀጥሎ "እና መሀንዲስነቱ ቀርቶ ጅል በመሆን ሥራ ገብቷል!" አለኝ።

ተሳሥቀን ስናበቃ ቀጥሎ ከተማዳር ለመጠጣት ተቀጣጠርን፤ ለግሌ የበዓል ስጦታ ደግሞ ሠጠሁኝ እና ሙሉ ታክሲ ለራሴ ቀጥሬ ወደቀጠሮዬ ተጓዝኩኝ።

ዘግይቶ ጆይ ሲደርስ ሡክሬ እየጠበኩ ነበር። እሱም እርካሽ ወይን አልሸጥ ሲል፣ ቀጣሪዎቹ "ለበዓል-ሥጦታ!" ብለው ሰጥተውት ስለነበር፣ ቀማምሶት ስንጨዋወት አመሸን።

ኬኔት በሥራው ቀኑን መዋል ሳያንሠው አምሽቶ ጭምር ደረሠ። ሰው ሁሉ ከእየቤተሰቡ ተሠባስቦ በዓል ሲያከብር እሱ የደረሰበትን የሁኔታ ግን በማስተዋል ገሀዱን ተጋፍጦ ጥቂት አዘን ብሎ ተቀላቀለን። "ባሪያ ነህ!" ጆጆ ቀለደ።

እየጠጣን፣ ሁሉም ሲሡከር የለመድንውን ጨዋታ አምጥተን ቀጠልን። ትንሽ ቆይቶ ደግሞ ስለ ጁዲት ተነሣ እና የሞሪሸስ ዜጋ የነበረው አሁን የተለያት ባሏንም አነሳን። እግረመንገድ የሞሪሸስ አምባገነኖችን ደግሞ አንሥተን እንጫወት ጀመር። አፍሪቃ ውስጥ ሀገር ይነሳ እንጂ አምባገነን፣ አማፂ ወይም ግልበጣ መጥቀስ እጅግ ቀላል ነው። ተሳሣቅን።

ኬኔት "ነገ ሥራ ስለምገባ ልረፍ!" ብሎ ሊመለስ አስቦ ሲናገር፣ ጆጆ ተገረመ። ዳግመኛ በባሪያነቱ ቀለደበት። "ጠንክሮ መሥራት እና መለወጥ እንጂ ባርነት አይደለም!" በማለት ኬኔት አምባረቀ። በበዓል ስራ ስለዋለ ተናዶ ይሁን፣ ንፁሕ ሀሳቡ ይሁን ብቻ ነደድ አለ። ቀጥሎ በቆመበት እንዳለ ስለሁለታችንም ወላጆች ሁለታችንም ጠየቀ። "ጆጆ ነጋዴ፣ እኔ ጠበቃ አባት ነበረን" አልን። እሱ ያልተማረ ድሀ አባቱ፣ እንደምናውቀው፣ የጆሞ ኬንያታ ስእልን ብቻ እንደተወለት እና አሁን እሱ ብዙ ጠንክሮ ሰርቶ አንድ ሺህ ዶላር ተቀማጭ፣ የተለያዩ ሱፎች፣ ከአንድ መኪናው ጋር እንዳለው ተናግሮ በመናደድ ቁጣው ጨመር-ብሎ ነገረን። ጥሎን፣ ሂሳባችንን ከፍሎ ወጣ።

ከገና በኋላ የቀረውን የድሴምበር ወር፣ እነዮዲት እና ናኦሚን እጅግ ናፍቄ በመቆየት ስጠብቅ ቆየሁ በወጣሁበገባሁ ቁጥር ቤቷን አሻግሬ እንቅስቃሴ ካሳየኝ መርመር-መርመር ሳፈርግ ከረምኩ። አሁን የህይወት መሠረት እንደሆነችኝ አምኜ እጅግ የበለጠ ናፈቅኩ። *ዘ ብራዘርስ ካማራሶቭን* በግሌ አንብቤ ጨረስኩት። በመጨረሻው በገጠመኝ ትርክቱ፣ ደጋግሜ አልቅሼ፣ ለናኦሚ ማስታወሻ በህዳጉ ፃፍኩበት። "ተማሪበት! አንድ ትዝታ ማኖር ህይወት ያድን አለ!" እሚለውን አሠመርኩላት። አከዬ፣ በእየቀኑ ምርጥምክርዎች (አፎሪዝም) እያከልኩ ፃፍኩላት። ከአዲስአመት ማግስት ኪራይ ልከፍል ስሄድ ገንዘቤ እማይሞላ እንደሆነ ተገነዘብኩ።

<u>**ምእራፍ ሰባት ፤ ኑሮ እና ሎጋን ሰርክል**</u>

*ሎጋን ሰርክል እጅግ ከፍተኛ የመለወጥ ሁኔታ ስለነበረው፣ የህንፃዎች አይጠቅሙም ብሎ ሠዎችን አፈናቅሎ ለማፍረሥ መዘገጃጀቱ፣ እና የገበያአው መቀነሥ አብረው እየተፋፋሙ ሄዱ።* ሲመሻሽም ሴተኛአዳሪዎች መንደሩ ወደመታፈር በመቀየሩ እየቀነሱ ሄዱ። በሂደት ገበያ ስለጠፋብአቸው የእሱም ገበያ አያስመሽም።

እስከ ቅርቡ ከኪራይ ወጪዬ መሸፈን ቀጥዬ፣ ጥቂት ለድንገተኛ የቢራ እማወጣው በለጥያለ የብር ቁጠባ-ዝግጅት ነበረኝ። የገና ሰሞን ግን ያንን ለወጪ በማዋሌ ሂሳቡን አዛብቼ ልዩነቱን መመለስ ስላቃተኝ አሁን እምከፍለው ጠፋኝ። ደግነቱ፣ እናቴ እንደለመደችው እና አንዳንዴ እንደምታደርገው ጥቂት ብሮችን ልካልኝ ነበር።

የገና እለት (ጃንዋሪ 7) እናቴ ጋር በላከችልኝ ብር አማካይነት ብቻ መደወል ችዬ፣ ወደእሷ ደወልኩ። ስለግጥም መፅሐፍ ስጦታው፣ ኤምሊ ዲኪንሰንን እንደእምትወድ ስለእማውቅ መላኬን ነገርኳት። በገጠርአማ የማሳቹሴት መንደር በባይተዋርነት ሳታገባ ኖራ በሞተችወቅት በቤቷ መሣቢያ ዉስጥ የታጨቁ ግጥሞቿ ተገኙ። እናቱ እምትሰማውን ትርክት ሁሉ በቅርበት በግልዮሽአዊነት (ፐርሰናሊ) ስለእምታስብ እጅግ ለገጣሚዋ አዘነች። በግል ተነጥሎ መኖርን እሚያሣምሩ ብዙ ግጥሞች የያዙ መሆኑን ገለጠ እና እንደእምትወደው አሣወቅኳት። “ገጣሚዋ ለብቻዋ በግጥሞቹ ብቻ ኖራለች። መነሻ ግጥም እንዲሆንሽ፣ “for each ecstatic instant” እሚለውን ምረጭ እና ለምን እንደእምትወጂው ይገባሽ አለ፣” አልኳት። ዳዊትም ልብሱ ሆኖት አለ አለችኝ እና ጥቂት ተጨዋውተን ስልኩን ዘጋሁት።

የነዋሪዎች ማፈናቀል በሰፈሩ ቀጠለ። ከፍተኛ የሰዎች እና አፍራሾቹ ጠብ እና ጩኸት ሲከተልም፣ ህግዘብ መጥቶ የማፍረሱን ሥራ በማስከበር አስቀጥሎ ሠላምን በጎን ለማስጠበቅ መጥቶ ማረጋጋት ጀመረ። በቀጣይም ቀን አንድ ሁለት ቤተኛ እንዲለቅቅ ሲገደድ አንዳንድ ሠራተኛ ግጥም ብሎ በኬኔት ሀሳብ መሰረት በተከፈትኩት ዴሊ ተሰብስቦ ፈጣንምግቦቹን መመገብ ጀመሩ። ሰው መሰብሰቡ እና ተፈናቃይ መብዛቱን ገከትሎ ገበያዬ ከቶ ድንገት ደርቶልኝ ቆየሁ።

አንድ ምሽት፣ አርፍጄ ስወጣ፣ የፈረሡ ቤትዎችን ተመልክቼ እሳቤአቸውን ለማግኘት ሞከርኩ። አንዱን የተለቀቀ ቤት ጎበኘሁ። የተዉት ዕቃ ቁሸሽ ብሎ ቀዳዳ ያለበት ቲሸርት ነበር። ድህ ሣሉ ለመባረርአቸው አዝኜ ለራሴም አንድቀን እንዳይመጣብኝ ፍራቻ ለመውለድ ተገድጄ ተመለስኩ።

ሚስስ ዴቪስ ወደሱቄ መጥታ ተመጋቢዎቼ ሲያወሩ እንደሰማሁት 'የመንደሩ ነዋሪዎች-ማህበር ሰፈሩን ከጥፋት ለማዳን ስብሠባ ሊያደርግ ነው!' አለችኝ። በእጅየተፃፉ የስብሠባጥሪ በራሪወረቀትዎች አዘጋጅታ፣ ይዛልኝ መጣች። “ወደሱቅህ ለመጣ መንደርተኛ ሁሉ አድል” ብላ ሰጠችኝ። የጃጁ አጥንቶቿን እንዳይብሱ እንደእምትፋለምላቸው ልማዷ ወተት ይዛ ወጣች። እኔ ግን መጨነቅ አልፈልግም። በርካሽነቱ የተነሣ ወደ ሠፈሩ ተማርሜ መጣሁ። አሁን ካስወጡኝ ተቀብዬ ልወጣ አቅጃለሁ። እንጂ በስብሰባውም በሰፈሩ መፍረስም መጨናነቅ አልፈለኩም።

**ምእራፍ አስር፣ የጁዲት እና ሎጋን ሰርክል ቤቶች**

*የተለያዩ የክርስትና እምነት ቤተክርስትያንዎች የነበሩ የተለያዩ የአምልኮ እምነትዎች እየተተካኩ መቀመጫአቸውን ባደረጉበት አሁን በተተወ እና ቅርስ ሊደረግ በታቀደ፣ ከቅርብጊዜወዲህ ባይተዋርዎች እና አዛውንቶች እሚሰበሠቡበት ብቻ የመሰለው ዕድሜ ጠገቡ ግንባታ የተቀጠረ ስብሠባው ተገናኘ። ከጓሮበሩ በኩል ስገባ መቶ በላይ ሰዎች ነበሩ።* ገብቼ በሩ ጋር እንደቆምኩ ስቃኝ፣ ጁዲትን ብቸኛ ነጯን ተሳታፊ ስመለከት ልመለስ አሰብኩ። ድንገት ከስንት ቀኖች በኋላ አየኋት። እና ልክ ልመለስ ስል ወይዘሮ ዳቪስ በዓይንዎች ከመድረኩ ሆና ያዘችኝ እና "ተቀመጥ" አለች። ጁዲትን አይቼ ፈገግታ አቅርቤ አልፌያት ሄድኩ። "የተማረችው የእነ ኤመርሰን ሀሳቦች እና ዲሞክራሲ አሰራር ያለ ከመሠላት ትገርምአለች!' ብዬ በልቤ እያሾፍኩ ፊትለፊት አካባቢ ተቀመጥኩ።

ስብሰባውን ሚስስ ዴቪስ ስለመንደሩ በአልሚዎች መተኮሩ እና ረዥም ዘመን የኖሩ ተነሺዎች እሚነኩ ሆነው መገኘትአቸውን ችግር ብላ በመጥቀስ ስብሠባውን ከፍታ መፍትሄ ፍለጋ እንዲተባበሩ በመጠየቅ መድረኩን ከፈተች።

ብዙዎች የሸመገሉ ተነስተው ተቃውሞ በማብዛት ሰጡ። አያይዘው፣ ስለእየግል አኗኗራቸው እና እሚያስጨንቃቸው የቤተሰብ ጥል ሁሉ ተናገሩ። ጁዲት ቀጥላ እድል ተሰጣት። "ስድስት ወርዎች ብቻ ብቆይም የሰፈሩ ጉዳይ ገብቶኝ አለ እና እኔም ይሰማኝ አለ!" ብላ ልክ ስትጀምር አንድ ድምፅ "አፍሽን ዝጊ!" አላት። ወዲያው ተቀመጠች። አቤቱታ (ፔቲሽን) እንዲዞር ደግሞ ከእዛ ተከትሎ ተበተነ። ቤተሰቦች አፈናቃዩ የአልሚዎች እንቅስቃሴ ቆሞ፣ ነዋሪዎቹ መኖር ይቀጥሉ እሚል ሀሳብ የያዘ ነበር። "እስከ ፌብሩዋሪ በቂ አቤቱታ ፈራሚ ቢገኝ ከከንቲባው ጋር ለቀጣዩ ሥብሰባ ልንመጣ ቃል እገባለሁ።" ብላ ሚስስ ዴቪስ ቀጥራን ወጣን።

ዴቪስ አብራኝ እስከሰፈር ልትጓዝ ቀረብ እያለችኝ ሥትዳዳ አምልጫት በመሄድ ጁዲትን ሰፈር አገኘኋት። "ከመጣሁ ጥቂት ቆየሁ። ፋታየለሽ (ቢዚ) ሆኜ አላገኘሁህም!" ብላ ናኦሚ ከእህቷ ልጅዎች ጋር ተደስታ ሥትቆይ በእዚያ ለእሚገኝ አዳሪ ትምህርትቤት እንደከተተቻት አሳውቃኝ ድንገት አስደነገጠችኝ። የአባቷን ስጦታ "ስጪልኝ" ብላኝ ስለነበር ልታስረክበኝ ቤቷ ገባን። ናኦሚ አባቷን አታቀውም። ሲገናኙ ከፍተኛ አጫሽ ስለነበር አፍጠረኑ አስጠላት። አትወደውም። ስጦታው ሲከፈት፣ የቆየ ታይፐመፃፊያ ሲሆን የቁልፎቹ ፊደልዎቹ የተቀረፁት በእንስሣት እና ቀለምዎች አሸብርቆ ነበር። ሰፈሩ ሲፈርስ የደራለትን ንግድ እንድትመለከት እና ጣፋጭ ሳንዱች እንድትመገብ ጋብዣት ተለያየን።

በማለዳ ጧት ወደሱቁ ስወጣ፣ ጁዲት መኪናዋ በድንጋይ ተመትታባት አየሁ።

ስቀርባት፣ መስኮቷ ተሰብሮ የተሰረቀ ግን ስለሌለ መስታወት ማፍረሱ ብቻ እንደታለመ አስተዋልኩ። ገብቼ ልጠራት ስል ከፍቶ ከበሯ አንድ ወንድ ወጣ። ፊቱ ጠይም፤ አረብ-አፍሪቃ ድብልቅነቱ የጎላ፤ ስለነበር ዕዉቅ የስነምጣኔ መምህሩ፣ የናኦሚ ወላጅ እንደሆነ አስታወስኩት። እና እማላውቀው ሰው ቢሆን ሁሉን ትቼ መመለስ አስቤ ሳለ ያን ከማድረግ ታቀብኩ። ለአያድ ዜናውን አረዳሁት። ጁዲት በላቃት መልኩ ጯኺ ሆና "ማነው?" ብላ ተጣራች። በፈረንሳይአዊ (ፍሬንች) "አንድ ሰውዬ መኪናሽ ተሰብሯል ይልሽ አለ" አላት። ሮጣ ወጥታ እኔን ስታይ ረጋ አለች። ከቤቷም ሮጣ በመዉረድ የሆነውን ስትመለከት ደንግጣ መጮህ ወይም ማልቀስ አቃታት። መአያ ባሏ፣ እሷን መርዳት አቅቶት ቆመ። ከእኔ እኩል እንደእኔ ሲመለከታት ተናደድኩ። እንደ ፈረንሳይአዊ (ፍሬንች) ሄዶ በማቀፍ በማፅናናት ሆኖ ለጆሮዎቿ 'C'est la vie' በማለት ወይም ሲጋራ አውጥቶ በመለኮስ ዳግ-ምላሽ (ሪአክሽን) መስጠት አለበት ብዬ አሰብኩ። ግድየለሽነቱን ተመልክቼ በመናደድ ተለይቻቸው አዘገምኩ። እየዞርኩ ስመለከት ያው እሷው ክው ብላ የቀድሞባሏም ለብቻው እንዳለ ነበር። ተናድዳ እሱም እንደራቀ፣ እየዞርኩ እያየኋቸው መበሳጨት ቀጠልኩ። ወደ ሱቁ ሳዘግም፣ ከፍተኛ ቅያሜ ይዞ አላስችል ብሎኝ እየዞርከጀ ተመልከቻተደ ክውታዋን እየተጋራሁ ከእይታቸው ጠፋሁ።

በሱቁ፣ ስለ ጁዲት መኪና ወሬው ግሎ አረፈደ። ከምኑም በላይ ስለእሷ ሲወራ የተረሳውን ያማረ የሆነውን ትልቅ ቤቷን እማያደንቅ አልነበረም።

መንደርተኛዎቹ ምንም እንዲህ ያለ ቤት ዉስጥ መኖር እሚቻል አይመስልአቸውም ነበር። ከሰዓትበኋላ ከመኪናዋ ድንጋዩ ቀጥሎ ወደቤቷ መስኮት ተወረወረ። ወረቀት አብሮት ተገኝቶ ሲታይ "ዉጪ" ወይም "ልቀቂ" እሚል ተፅፎ ተገኘበት። በመጨረሻ፣ ፖለቲካአዊ ጉዳይ እየሆነ መጣ። አንድ አዛውንት በሱቁ አካባቢ እሚንቀዋለል፣ "ሁሉን አየሁ ወጣትዎች ናቸው፣ ወርውረው በእርጋታ ዘና ብለው ሄዱ" ሲል ሰማሁት። ሚስስ ዴቪስ መጥታ በወሬው ተጠምዳ እንዲሁ መሰል ተባራሪ ወሬዎች አወራችኝ።

በማግስቱ፣ በ ኒውሀምፕሻየር  አቬኒው እና 12ኛ ጎዳና ጥጋት እሚገኘው የኒውሀምፕሻየር ታወር መስኮቱ ተመትቶ ተገኘ። በ 1920ዎቹ የስነምጣኔ መበላሸት ወቅት ተገንብቶ የተረሳ እና በበቀለበት ቁጥቋጦዎች ሴተኛአዳሪዎች ከ 'ዲር ጆንዎችአቸው' ጋር ፈጣን ስራዎችን እዚያው እሚሠሩበት የሆነ ነበር። በሱቁ የተስተናጋጆቹ ወሬ ቀጥሎ ዋለ። የሁለተኛው ጡብ ወረቀት ደግሞ 'የስድስት ሰዎች ቤተሰብ ስላፈናቀሉ የተወረወረ ቅጣት' ይል ነበር። ሁለተኛ የእለቱ ወሬ ደግሞ፣ በ 13ኛ መንገድ ቆሞ የነበረ መርሴዲስ መኪና ጎማው ተቀድዶ ተገኘ እሚል ሆነ። ማታ አምሽቼ ሱቁን እየሰራሁ ወሬዎቹን ማድመጥ ቀጠልኩ። ወጣት እና ትልልቅ ሰዎቹ ሰፈርአቸውን በተሳትፎአቸው ለመቆጣጠር ብለው ተሰብስበው ብዙ ማውራት ተያይዘውታል። አፍሪቃ እና አዲስአበባ እንዲህ ባሉ በማህበረሰብአቸው ለመሳተፍ ፈልገው በአሚያምፁ ወጣቶች እንደተሞላ እና ከእነኬኔት፣ ጆ፣ እና እኔ እምናቀው ከዕውቀት የበለጠ ሆኖ በከበደ ሀቅነቱ ነው። ጥቁርበጥቁር ለባሽ ጡብ ወርዋሪ ወጣቶቹም እንደተባለው ሊኖሩ እና ሰባሪዎቹ ሊሆኑ ይችል አሉ። ብቻ ማህበረሰብአዊ ተሳትፎ እኔ ሱቅ ወቅት ጠብቀው በእሚኮለኮሉ እና ወሬ በእሚያሳድዱ በእዚህ መንገድ እሚከወን ጉዳይ አይደለም።

ኩለሌሊት ድረስ ሰርቼ ቤት ስመለስ፣ ጁዲት ቤቷ በሙብራት አብረቅርቆ አያድ ጋር በከፍተኛ ጩኸት ስትሰድበው እሱም ሲመልስላት አደመጥኩ።

ጧት ሱቁ ስመጣ ጡብ ቤቴበር ላይ ምንም አደጋ ሳያመጣ ተጥሎ አገኘሁ። በርከፍቼ አስደገፍኩበት። ወዲያው ጁዲት ገባች። የናኦሚ ደብዳቤን አስረክባ “ያን ቀን መኪናዬ ባይመታ አቀብልህ ነበር” አለችኝ። የተማሪቤት ጦማር አድራሻዋን ሰጥታኝ ጦማር በመፃፍ ልመልስላት ተነጋገርነደ። ጁዲት ከባሏ ጋር እስኪነጋጋ አካባቢ ስትጣላ ነበር። በመስኮት ሣደምጥ ነበር። ግድየለሽ እና ለልጁ እማይጨነቅ፣ በልጁ እሚጠላ መሆኑን ጁዲት ስታነሳበት አያድም እየጮኸ ምላሽ ይሰጥ ነበር። የተለመደች አሜሪካአዊት ሴት እንደሆነች እና ሆንብላ ያማለለችው እንደሆነ፣ ልጁን ደግሞ እሚጠላት በከፊል ከጁዲት የመጣውን የማንነቷን ጎን ለይቶ ብቻ እንደሆነ እንደሆነ አሣወቃት። እንዲህ ሰሞኑን ንብረቶቿ በተጠቁበት ቆሻሻ በሆነ ሠፈር ህፃን ልጇን ማምጣቷንም ጠቅሶ ከሠሰ። ሲጨቃጨቁ እንዳደመጥኩ ነጋግቶ ተኝቼ አሁን ጁዲት አዝና አያድን ከ ኮኒክቲከት በማምጣቷ እና ከእሱ ጋር በመገናኘትአቸው አለመደሰቷን ነግራኝ ለእራት እንድንቀጣጠር አሳሠበችኝ። ማቅማማት አቃተኝ እና ለነገ ማታ ተቃጥረን ወጣች።

የናኦሚ ደብዳቤውን ሳይ እንዳሰብኩት ናኦሚ እኔ ጋር ስትመላለሥ የኡሮዬ አካል ሆና በእኔ ዋጋአጊንታ እንደነበር ተረድታው እንደነበር አወቅሁ። በፃፈችልኝ 'አሁን ስለተለያየን ብቻህን እንዳልሆንክ ተስፋ አለኝ!' አለች። ቀጥላም፣ 'እዚህ ባለሁበት ሰው ቢኖርም እንደአንተ ምርጥ ግን አይደሉም!' በማለት ነግራኝ፣ ቀጥዬ እንድፅፍላት ገልፃልኝ ተሰናበተችኝ። በመዳፍብር-(ካሽ)-ዘጋቢው (ሬጂስተር) ቂጥ አኖርኩት፤ 'ምናልባት ደግሜ ካነበብኩት እዚችው ስፍራ ቆሜ ላነበው ነው የምፈልገው' ለራሴ አልኩ።

እኩለቀን ሲል፣ ሱቅ ከመሄድ ወደቤቴ ተመለስኩ። በኋላ ሱቅ ገብቼ አመሸሁ። ማታ፣ ጁዲት ቤት መቃጠል ቀደም-ባለ-ጊዜ፣ ኬኔት እና ጆ መጥተው ጆ የሰረቀውን ወይን ከአዘጋጀነው ተርኪ ሳንዱች አዳብለን እየተመገብን፣ የመንደሩን ሁኔታ እኔ አብራራሁላቸው። የጡብ ዉርራዎቹን፣ ጥቁር ለበሱ እሚባሉትን ይህን ከዋኝ ሰዎቹን፣ የአያድን ሁኔታ፣ ወዘተ. ነገርኳቸው። “ይህ ለሰፈሩም ላንተም መጥፎ ምልክት ነው” ሲሉኝ ገበያዬ ግን ጨምሯል አልኩ። ግን አሁን በርግጥ ቀንሶብኛል። “የምነደሩ መጨነቅ ነው ገቢህን ያመጣው” አለኝ ጆ። “ዛየር ሰው ሲጨነቅ ወጪ ያወጣ ነበር” ብሎ ጆ ያንን ያብራራ ቀጠለ። “አማፂዎች መጥተው 'ጨቋኝዎችአችሁን ይኸው ያዝንልላቹህ!' ሲሉ የመንደሩ ሰው ይገረም አለ። 'ጨቋኝ ነበረን እንዴ?' ሲላቸው ለማረጋገጥ አንድ አምስት ሰው እዚያው ይረሸኑላቸው ነበር። 'አህ ተጨቋኝ ነበርን!' ብለው ተደስተው ብር ይከፍላሉ፤ በጣም የተደሰተ አንዱ አንድጊዜ ሚስት እና ልጁን ሁሉ ሰጣቸው። 'የአፍሪቃ ጉዳይ እንዲህ በልጅዎች እሚደረግ ጦርነት እና አመፅ ይበዛው አለ' ብሎ ጆ ማብራሪያውን በሌላ ድምዳሜ ፈፀመው። በስድሳዎቹ ድሮ ተስፋ ነበረን፣ አለም እና አፍሪቃ ነፃ ወጥቶ ወደአንድ ነገር እየተጓዘ ነበር። ዛሬ ግን እኒህ እሚረብሹት ምንም የሌልአቸው ልጆች ናቸው። ጆጆ የሩዋንዳ ማጭድ፣ የፖኪስታን ድንጋይ፣ እዚህም የተነሱት እና እኔሱቅ ዘንድ የደረሱት ጡብዎች 'የእኛ መገለጫ ናቸው!' አለን። “ጡብ ነን!” እሚለውን ሀሳቡን አሳበቀልን።

ያኔ ስንወያይ ነበር፣ ድንገት የእሳት ማጥፊያ፣ ህግዘብ (ፖሊስ) እና አምቡላንስ መኪናዎች ጩኸታቸው ሰፈሩን የቀወጠው። ጆጆ የአፍሪቃ ጦርነትዎች በህፃናት መከወኑን ሊያሳይ የሠላሳ አመትዎች ጦርነትዎችን መረጃዎችን ሲያሣላ፣ የአደጋ መከላከያው ድምፁ ከውጭ ወደሱቁ መግባቱ ከባድ ሆነ። የአፍሪቃን መንግስትዎች ግልበጣ፣ እረሀብ እና የልጅዎች ዉጊያ ተሳትፎ ስንወያይ አፍሪቃ ድረስ ያልሸሸ፣ እዛው የእራስአችን ህይወትም ትራጂዲ እንዳለው በተግባር ለመመልከት መገደድ ጀመርን። የእምንነጋገረው ሁሉ የአህጉሩ መከራ በመጨረሻ የእራስአችንን መከራ ለመርሳት የተደረገ ሆኖ ሰንብቶ አሁን ሁለቱም

(የአፍሪቃ እምንለው እና የእኛም ገሀድ) ችግርዎች ወደ መጋጠም (መመሳሠል) ጀመሩ። መንደራችን በፍርስራሽ ቀጥሎ በመልሶማጥቃት ጥፋቶች መታመስ ጀመረብን።

ጁዲት ከባልደረባዎቿ እራት መከወን ላይ ሳለች፣ ቤቷ መንደድ ጀምሮ፣ ሰው ተሰብሥቦ እየተመለከተ ነው። ምንም አልዳነም። እሳትአጥፊዎቹ ሱቁ ገብተው የተናገሩት ቢኖር፣ የቀረውን ወለል፣ እሷ ስላልነበረች እንዳላዳኑት ነው። አምስት አመትዎች ቀድሞ ሰው በሎጋን ሰርክል ተተኩሶበት ተገድሎ የመንደሩ ሰው እንደተሰበሰበው አሁንም ሰው ተሰብስቦ ይህን ልእለቤት ሲምቦገቦግ ተመልክቶ፤ ሁሉም አራት ወለልዎች ወድመው ጁዲት ደረሠች። በዘገየምሽቱ ደርሳ ተስፋቆርጣ ስትንቀሳቀስ እሚደርሰውን ይህን እምታውቀው የነበር ይመስል ነበር፦ ጊዜዋ በሎጋን እማይዘልቅ ጊዜአዊ የነበረ እንደነበር እና ሌላ መኖሪያ ስታስብ እንደነበረ አሳበቀ። ስለቤቷ ማዘኑን ገልጬላት ተለያየን።

የመንደሩ አምስት ወርዎች አካባቢ የረዘመ ቆይታዋን የመጥፎ ህልም ያክል፣ ልትተወው እንደምትችል አሰብኩ። እነኬኔትም ከሱቁ ከእኔ ጥቂት አውርታ አዝና ስትወጣ አይተዋት ለመጀመሪያጊዜ ገና በዓይን አወቋት። ምሽቱን ጉዳይዎች ስናወጣ እና ስናወርድ በሱቁ አመሸን። ያን ማን እንደከወነ ስንጠያየቅ ቆየን። በማግስቱ ፍራንክሊን ሄነሪ ቶማስ የተሰኘ የቅንጡ ቅኝገዥ ስም የያዘ አዛውንት ወንጀሉን እንደከወነው በይፋ ተነገረ።

ጥቁርለበስዎቹ ወይም ሌላዎች የተባሉት አሉባልታዎች ቀርቶ፣ የጡብ እና እሳቱ አደጋ ፈጣሪ የሆነው ይህ ሽማግሌ ሰው፣ የተሰረቀ የትመ. (ትእይንተመስኮት = ቲቪ) ግንኙነት ለመንደሩ በትክክል መግዛት ላልቻሉ ድሀዎች ይሸጥ ነበር። በሎጋን ሰርክል ድሀ እና በሀምፕሻየሩ አፓርታማ ከሁለት ልጅዎቹ እና ሚስቱ ጋር ለአስራስምንት ዓመትዎች በአንድ ክፍል ይኖር የነበረ ሰው ነው። አብሮ የተለያዩ የጥገና እጅስራዎችን በመሠራራትም ይታወቅ ነበር። ያን የእሚነለርበት ባለ አንድመኝታ ቤቱን ባለፈው ዲሴምበር ሊዝ አለቀበት ብለው ሚሶ ዋጋ ጨምረውበት ሂሳቡን ክፈል ሲባል ነበር ያቃተው። ሲያስለቅቁት እጅግ ተናደደ። ወደ ጊዜአዊ መጠለያ እሱ ሲገባ ሚስቱ እህቷ ጋር ልጆቻቸውን ይዛ ተለየችው።

ጁዲትን ቤቷን አቃጥሎባት ከወጣች በኋላ በሳምንቱ የእጅስራ እቃዎቹን በሻንጣው ይዞ የተቃጠለ ቤቷ ተደብቆ ሲገባ ህግዘብ ያዘው። ቤቱን አድሶ ሊኖርበት አስቦነበር ማለት ነው። ይህ ጀዝባ ቀውስ። ቀውስአዊ-ቅዠት (ዲሉዥን) ነበረበት። ህግዘብ ሲጠይቀው 'ሰው አለመኖሩን አረጋግጬ ነበር ክብሪቱን የለኮስኩት' ብሎ ተናዘዘ። በ *ዋሽንግተን ፖስት* የወጣውን ይህን የአደጋውን ወንጀለኛ ዘገባ አንብቤ ስጨርስ ከተለጠፈው ከሰውየው ፎቶ ጋር ምስሌ ተቀራራቢ ሆኖ አገኘሁት። መላጣነቱ እሚያመሳሥለን እና እድሜዬ ጥቂት ሲገፋ በተለይ እንደእሱ እምመሥል መሆኑን አስተውዬ ምስሉን አጠገቤ አቆየሁት።

ህግዘብ (ፖሊስ) በሎጋን ሀውልት ጎን በመኪና ሆኖ እየቆየ መንደሩ ጥቂት ቀኖች ያን ሰሞን ተጠበቀ። ብዙ ሳይቆይ ግን መኪናው እና ህግዘቡ ሄዱ። የሎጋን ሀውልት እና ሎጋን ሰርክል ለብቻቸው እንደለመዱት ቀረ። ከእሳቱ በኋላ ሱቁን ያለደንብ ባሻኝ ጊዜ ለአንድ ሰሞን ከፈትኩ።

እንደ ኬኔት አባባል ላዘጋው ወይም ደንበኞቼን ላጣ ብዬ አልነበረም። ለናኦሚ በመልስ ደብዳቤ እንደፃፍኩት እና የአጎቴን ምርአዊ (ሲሪየስ) ደብዳቤዎች መሰለ በማለቱ እንዳልላኩላት ደብዳቤዬ፣ በስርአቱ እማልከፍተው ናኦሚ እና ጁዲት ስለሌሉ ነበር። እነሱ ፈፅሞ በሌሉበት ሰፈር ጧት መንቃት ደብሮኝ፣ ሱቁንም ከእኔ ሌላ አንድ ሰው እንኳ ተጨንቆ ካልወደደው መክፈት እንደእሚደብረኝ ገለጥኩላት።

በመጨረሻው የመንደሩ ጉብኝቷ፣ ጁዲት ቻው ልትል ጊዜ አመቻችታ ሱቄ መጣች። ከሰዓቱን ብቻዋን የወደመ ቦታውን ላለማየት ስለፈለገች ሱቅ ዘግቼ አብረን ሄድን። 'ዳግ-ገንቢው' (ሪቢውልድ) ብዬ ለማለት ያክል ብነግራትም "ያለፈጊዜዬ ላይ በወጥመድ መያዝ ነው" ብላ ስለአዲስ ህይወት ጅማሮ በማለት እንቢ አለችኝ። ከ ዴሞክራሲ ኢን አሜሪካ እሚለው ተከታታይ ፅሑፍ ጥቅስ - በፅሑፏ የተጠቀመችበት - ሰጠኋት። እምትወደው የተጠቀመችበት ጥቅስ ነበር። በጠቅላላው፣ 'በ ዲሞክራሲ ሀገርዎች መሀከል፣ አዳዲስ ቤተሰቦች ያለማቋረጥ ይፈጠራሉ፣ እንዲሁ እሚጠፉም ደግሞም አሉ። ብቻ የቀረው እሚለውጥአቸው ነው። የጊዜ ሚዛን ግን የጠፉትንም የተሰበሩትንም እሚከትት ነው!' ይላል።

"አንድ ጊዜ፣ ለጊዜውም ቢሆን አዲስቦታ አጊንቼ ስሠክን መጥተህ ትቀላቀለን ይሆን አለ" አለችኝ። ድጋሚ በሚገናኝ የህይወትአችን ሃሳብ ተስማምተን ጉዳዩን ዘጋንው። ተለያየን።

'በሁለት ዓለምዎች መሀከል የተያዘ፣ ብቻውን ኖሮ ብቻውን ይሞት አለ!' በእሚለው ሀሳብ ፀናሁ። በአባቴ ትዝ ያለኝ ተረት ላይ ያያንን መጨመር ፈለግሁ። አባቴ 'በዛፍ ቅርንጫፍ የተያዘች ወፍ ሁለቱንም ክንፎቿን ትበላለች!' ብሎኝ ነበር። አሁን ግን፣ የሁለት ዓለምዎች ህይወት ስላሳለፍኩ የእኔው ህይወት ከሁለቱም አለመሆኑን አየሁ። ሱቅ ስላለኝ እና የእኔ እምለው

ንብረት ስላለኝ ያም ንብረቱ ፍፁም እሚባል ባይሆንም እንደመንደሩ አንድአንድ ሰዎች ስላልፈረሰብኝ እና ዛሬም አብሮኝ ስለቀረ መደሰቴን ግን አተዋልኩ።

ነገርን እንደመረጥንው መመልከት ወይም መተርጎም እንችል አለን። ከአመዳማው ከሰላማው ፍርስራሹ የጁዲት ቤት ወደቤቴ ተለይቻት ስሄድ በቀና መንፈስ ወይም እስከቤቴ ያለውን ስምንትመቶ አካባቢ እርምጃዎች በተሸነፈ ስሜት ማዝገም እችላለሁ። መምረጡ የኔ ፋንታዬ ነው። ሁሌም የመጀመሪያዋ እርምጃ ከባድ ናት። ግን ቀናውን መመልከት የግዴታዉዴታዬ ነው። ጨከኜ ስጀምራትም ቀለል ትላለች። እና የከሰሉ ደረጃዎቹን በተስፋ ልራመድ አሰብኩ። መቶበመቶ አልከሰርኩም፣ ባለኝ ተደስቼ ወደፊቱን አምኜ በእርጋታ ልኖር፣ ሁኔታውን እና እርምጃዬን በቀና ልተረጉመው እና ላዘግም መረጥኩ።

